ወደ ዴርቶጋዳ እንኳን ደህና መጣችሁ። የላይኛው ዶራሲ መልካም ፈቃድ ሆኖ ያ ክንፋም መልአክ እንደ ገና መጣ። የቀማኝንም ላባ ከክንፉ ላይ ነቅሎ መለሰልኝ። ወትሮም ዣንቶዣራ የሚል ቃል እንድፅፍ አዘዘኝ..... እጄን ታጥቢም እንዲህም ሆነ። ከሆነውም ሁሉ አላንዳች የሆነ የለም።

በዴርቶጋዳ አሀዱ፣ በራማቶሓራ ክልኤቱ የተባለው ተከታታይ ልቦለድ እነሆ የላይኛው ዶራሲ ፈቃድ ሆኖ በዣንቶዣራ ተሰልሷል። ይህ ተከታታይ ትረካ በቅደም ተከተል ሲቀመጥ የሚከተለውን ይመስላል። *ዴርቶጋዳ- ራማቶሓራ- ዣንቶዣራ*።

ይህን ሶስተኛ ክፍል አዘጋጅቼ ለማቅረብ በምጥርበት ወቅት፣ ሁለት *ተልሚድና ተክርቸም* የተሰኙ ልቦለዶችን በመሀል አሳትሜያለሁ። እነዚህ ሥራዎች ደግሞ ራሳቸውን የቻሉ እንጂ የዴርቶጋዳ አካላት አለመሆናቸውን ለአንባቢዎቼ መግለጽ እፈልጋለሁ።

ስለተ-ወንዝ ትረካው ቀጥሏል። ወንዝን ያስተውሏል፣ ኸረትን ልብ ይሏል።

ኸረት ሲጠነሰስ የዕንባ ጠብታ ከምታክል ምንጭ ነው። ምንጯን አያሌ ጠብታዎች እየተቀላቀሏት እየበዛች ትሄዳለች። ኸረቱ ይወለዳል። ገባር ኸረቶችም ይቀላቀሉታል። ታላቅ ወንዝ ይሆን ዘንድም አያሌ ወንዞች ይገብሩታል። ኸረቱ በገበሩለት ኸረቶች ልክ እየሰፋ ይሄዳል። ወንዙን የፈጠሩትን ኸረቶች ታሪክ መተረክ ተገቢ ነው። ወንዙ የንኡሳን ኸረቶች ውጤት በመሆኑ ታሪካቸው ታሪኩ ነውና ያለነርሱ ታሪክ፣ ታሪክ የለውም። እንዲሁም *ራማቶሓራ* በክፍል አንዱ *ዴርቶጋዳ* የተዋወቅናቸውን ገፀ-ባህርያት እነ ሻጊዝን፣ እነ ሚራኸን፣ እነ ጌራን፣ እነ ሜሮዳን፣ እነ ሲጳራን ወዘተ. ብቻ ይዞ አልተጓዘም። ራማቶሓራን ስንገልጥ እነ አባባ ደጋጎን፣ እነ ፕሮፌሰር በርናባስን፣ እነ ማርዬ ዋቆ ማርዬን፣ እነ አድያምን የመሳሰሉ

ያው ዕርቃኑን ይገፈፋል!

ሲ...............ጥ!

## ምዕራፍ ዜሮ

ሸዊያ አባላት አዕምሮ ውስጥ ብዙ አስፈሪ ክንዋኔዎች በፊት፡፡ በሶስት አባላት አዕምሮ ውስጥ ብቻ አለ ክትመታት በፊት፡፡ በሶስት የተቀበረ ከፍተኛ ምስጢር፡፡ በአንድ ወደኛው በምስጢር የተቀበረ ክፍተኛ ምስጢር፡፡ በአንድ ወዲያኛው በምስጢር እጅግ ረቂቅ የሆነ ወታደራዊ ስልጠና በማይታወቅ ተራራ ውስጥ በህይወት የተረፉት አስራ ሁለቱ ከሚሰጣቸው 29 ሰዎች ውስጥ እደገኛነት የተነሳ አልቀዋል፡፡ ብቻ ነበሩ፡፡ ሌሎቹ ከስልጠናው ተራራ ውስጥ በክብር ተቀብረዋል፡፡ አስከፊናቸውም በዚያው ለመሞት፣ ለመሸሽ ሳይሆን ጥቅን የተረፉት ለመግረዝ ሳይሆን ብቃት፣ ጥራትና ንቃት ያላቸው ሆነው ሳይቀር ለማባረር፣ ያልወሰዱት የስልጠና ዓይነት አልነበረም፡፡ ተመርጠዋል፡፡ ያልወሰዱት የቅብ (የሚኪና) ሰዎችና የቲአትር ለመመሳሰል እውቅ በሆኑ የሙዚቃ መሣሪያዎችን፣ ቀልዶችንና ሰዎች፣ ለማሞኛ ብዙ በየሀገሩ ·እየተወሰዱ ሰልጠነው ስንጥበባዊ ስልጠናዎችን ሜካኒክነት፣ ሹፍርና፣ የትኛውንም አውሮፕላን ተመልሰዋል፡፡ መካኒክነት፣ ጢያራ ቢያጡ አሞራ ይጋልባሉ ተብሎ ማብረር ብቻም ሳይሆን፣ ከውጊያ ስልት እስከ ሎጂስቲክ ተክነዋል፡፡ ተነግሮላቸዋል፡፡ ሁሉንም የተፈጥሮ ሳይንስ በገፍ ኬሚስትሪ፣ ፊዚክስ... የአሜሪካው 'ዴልታ ፎርስ' እንኳ እንዲህ ሰልጥኖና ጠጥተዋል፡፡ ተክኖ እያውቅም ከተባለላቸው ከእነዚህ ልዩ ኃይሎች ውስጥ፣ ሚራዥ የመጨረሻውን ፈተና አልፎ ተመርጧል፡፡

ለመመረቂያ ዕሁፋቸው የሠሩት የጦር መሳሪያ ግን በምስጢር እንዲያዝ ተደርጓል፡፡ የመሣሪያውን ስምም እንደ ተግባሩ 'ሳቅ በሳቅ' ሲሉ ሰይመውታል፡፡ የአሠራር ቀመሩ በምስጢር ቢያዝም በዚህ መሳሪያ የተመታ ሰው እየሳቀ እንዲሞት ተደርጎ የተሠራ ነው፡፡ እያሳቀ የሚገድል መሳሪያ፡፡ እያሳቁ መግደል፡፡ እየሳቁ መሞት፡፡

"ሞት ቀለል ማለት አለበት፡፡ ጥንት በድንጋይ መወገር፣ በኋላ በጦር መወጋትና በሰይፍ መቀላት፣ አሁን ለዓዕር በሚተው ጥይት መበጥረቅ፣... ይህ ሁሉ መቅረት አለበት፡፡ ሲቻል... ትልቁ መሣሪያ ጭንቅላት በመሆኑ በእርሱ መዋጋት የመጨረሻው ቴክኖሎጂ ነው፡፡ ይህ እስከሆን የጥይትን ቋንቋ፣ ቋንቋው ያደረገውን ዓለም፣ እያሳትን እንዋጋዋለን፡" ሚራዥ ልዩው መሣሪያ በተመረቀበት ወቅት የተናገረው ነበር፡፡

# ፩

## አዲስ ዘመን፥ኢትዮጵያ

ተራራው ተከቧል፡፡ በተራራው ክርስ ምድር ውስጥ ያደፈጡት ምስጢራዊ ሰዎች ግራ ተጋብተዋል፡፡ ከተራራው ውጪ የነበሩትም የሜዞ ቅቤ ሆነው ቀርተዋል፡፡

ሚራዥ ለመጀመሪያ ጊዜ በቁጣ ወደ ሻጊዝ ተመለከተ፡፡ በግንባሩ ደም ስሮች ውስጥ አንዳች ነገር በደምፍላት ሲራወጥ በግልፅ ታየበት፡፡ ምድር ለምድር አፈር እንደሚገፋ ፍልፈል ንዴቱ ግንባሩን ቀዶት ይወጣ መሰለ፡፡

"ራሳችንን መከላከል አለብን! ተራራው እስካፍንጫቸው በታጠቁ ኃይሎች ተከቧል፡፡ ከዚህ ተራራ እንኳን ሰው ጢስ እንኳ ለማምለጥ አይቻለውም!..." የሚራዥ ከንፈሮች በእልህ ተንቀጠቀጡ፡፡ ከቃላቱ ጋር የሚወጣው እንፋሎት የሻጊዝን ፊት እስኪለመጥጠው እስካፍንጫው ተጠግቶ በኃይል ሲናገር ሌሎቹ በድንጋጤ ክው ብለው ተመለከቱት፡፡ ከስንት አንዴ እንዲህ እንደ መብረቅ እንደሚባርቅ ከነሲጳራ በቀር ሻጊዝ ራሱ እንኳ የተገነዘበው አልመሰለም፡፡

ሻጊዝ ምንም መልስ አልሰጠውም፡፡ ሊሰጠው የሚችለው መልስ እንደሌለውም፣ ሁለቱም ያውቃሉ፡፡

"ስማኝ ሻጊዝ! ... በዚህ ተራራ ውስጥ ..." ሚራዥ ዙሪያውን ቃኘ፡፡ የሁለቱን ንትርክ ለመስማት ብቻም ሳይሆን፣ ተራራው መከበቡ ከተረጋገጠ በኋላ ግራ የተጋቡት አያሌ የተራራው ውስጥ ነዋሪዎችን ተመለከተ፡፡ "በዚህ ተራራ ውስጥ ከመላው ዓለም በስውር የተሰባሰቡ አእምሮዎች እንዳሉ ታውቃለህ፡፡ እንኳን ኢትዮጵያ አፍሪካ እንኳ ይህን ያህል የላቀ አእምሮ ድምር የላትም፡፡" ትንሽ ፈቀቅ ብሎ ለሻጊዝ ጆርባውን

ሰጥቶት ቆመ፡፡ ትንፋሹን ለመሰብሰብ ታግሎ ሁለቱን እጆቹን ዙሪያውን በከበበው ህዝብ ላይ ዘረጋ፡፡

“ይህ ሁሉ አእምሮ! ይህ ሁሉ ጭንቅላት እዚህ ተራራ ውስጥ እንደ ንፍሮ ሲቀቀል ማየት ትፈልጋላችሁ? ለዘመናት የለፋንለት፣ ለአፍታ ያልተኛንለት ህልማችን ከንቱ ሆኖ ሲቀር አምናችሁ መቀበል ትሻላችሁ?”

ከዚህ ዘራፍ አከል ማስጠንቀቂያ በኋላ፣ ሁሉም በየፊናው ይከራከር ጀመር፡፡ እንደ መስከረም ድንጉላ፣ እንደ አበባ ወቅት ንብ፣ ሁሉም ሲያጉተመትም የተራራው ክርሰ ምድር የተነካ የንብ ቆፎ መሰለ፡፡ በሥራ ላይ ተጠምደው የነበሩት ሳይንቲስቶች ከየምድብ ሥራቸው እየተነሱ መጥተው ግርግሩን ተቀላቀሉ፡፡

“እንከላከል! ራሳችንን እንከላከል፡፡”

“አይሆንም! ..... እስከዛሬ የለፋነው ሽምቅ ተዋጊ ለመሆን ነው እንዴ?”

“ተራራውን ሰብረው ከገቡ አንድም ሰው አይተርፍም!”

“እረ ተው ጎበዝ! ድርጅቱን ወደ ሽምቅ ተዋጊ ቡድን ልትለውጡት ትፈልጋላችሁ?”

“ተራራውን ሰብረው ከገቡ የማረኩትን እንኳ አይምሩም፡፡ ሁላችንንም ወደ አመድነት ነው የሚለውጡን፡፡”

“እንደራደራቸው!”

“ምን ይዘን ነው የምንደራደራቸው?”

“አዲስ አበባ ውስጥ ያሉት አባላት አንዱን ባለሥልጣን ያፍኑ! እነ ሜሮዳ እነ ጌራ እዛ ምን ይሰራሉ? ይህ ተልዕኮ ለሜሮዳ ይሰጥ! እሷ የምታደርገውን ታውቃለች”

“ጠቅላይ ሚኒስተሩን ካልሆነ ሌላ ባለሥልጣን ቢታፈን ምን ዋጋ ሊኖረው? እሰየሁ አበጀሁ ብለው የታፈነውን ባለሥልጣን ቀቅላችሁ ብሉት ቢሉንስ?”

በዚህ ጊዜ አንድ ሰው የሚራኝ'ን እጅ ይዞ እየጎተተ ከግርግሩ መሃል አውጥቶ ከወሰደው በኋላ በለሆሳስ አንድ ነገር አንሾካሾከለት፡፡

“በኢንጂነሩ እንደራደር” አለ፣ የሚራኝ'ን ትከሻ እንደጉርና እየናጠ፡፡ “ሲ.አይ.ኤዎች በዚህ ከበባ ውስጥ እንጻሉበት

አትጠራጠር፡፡...... የኛዎቹ ሰዎች ይህን ህቡዕ ቡድን ሊደርሱበት አይችሉም፡፡ የሲ.አይ.ኤዎች እገዛ አለበት፡፡ ሲ.አይ.ኤዎች ደግሞ የሚፈልጉት ቫይዝን ብቻ አይደለም፡፡"

"ሌላ ደግሞ ምን ይፈልጋሉ?"

"ሌላ ደግሞ የምርምር ማዕከሉ ይዞት የመጣውን ጥቁር ሳጥንና በውስጡ ያለውን ረቂቅ ቴክኖሎጂ ጭምር ቀን ተሌት ፍለጋ ላይ ናቸው፡፡ ካሎስ አሳሞስ በቫይረሱ እና በጥቁሩ ሳጥን ከመደራደር በቀር ሌላ ምንም አማራጭ የለንም፡፡"

"እሺ በስመ አብ በል!... ይህማ የማይሆን ነገር ነው!"

ሚራኝ በስውየው አባባል ክው አለ፡፡ "አላደርገውም!"

"ለምን ሚራኝ!" አለ ሰውየው እንደገና የዞረውን የሚራኝን ፊት እየፈለገ፡፡ "በዚህ ሰውዬ ጦስ አይደለም እንዴ ቁጥር አንዱ የዴርቶጋዳ ማዕከል የጋየው? ያ! ... የፎርጅዱ ቫይረስ ጭንቅላት ፈንድቶ አልነበረም ህልማችን ሁሉ የወደመው? አሁን ደግሞ ይኸው ተከበናል፡፡ ያ ሁሉ የተራቀቀ ቴክኖሎጂ ብቻ ሳይሆን፣ ያ ሁሉ ተመራማሪ ጭዳ የሆነው በማን ጦስ ነው? በቫይረስ ምክንያት አይደለም? ነው፡፡ ይኸው እዚህ ያሉት ዶክተሮች እንኳንስ የፊት ቀዶ ጥገና አድርገው ቆዳን እንደልብስ ሊቀይሩ ይቅርና የሚሮጳን እጅ እንኳ ከመቆረጥ አላዳኑም፡፡ ከስንት ጊዜ ማንሰራራት በኋላ ብናቆጠቁጥም ይኸው በእሱ ምክንያት ይህን ተራራ ወደ እመድነት ሊቀይሩ ምላጭ ለመሳብ ትዕዛዝ በሚጠባበቁ እጆች ተከበናል፡፡"

"አይሆንም! የምትለኝን እንኳን እኔ አንተ ራስህ የምታምንበት አይመስለኝም፡፡" ሚራኝ ሰውየውን በቁመበት ጥሎት ሄደ፡፡ የስውየው ድምጽ ግን ከኋላው ተከተለው፡፡ የዛቻ ድምጽ፡፡

"ግዴለም! ይህ ተግባር የእኔ ይሆናል! እንደ ፋሲካ ዶሮ ከንፍና ከንፉን ይዤ አስጣችዋለሁ!"

ሚራኝ በደምፍላት ወደ ሰውየው ተመለሰ፡፡

"ምን!? ለመሆን የከበቡን ሰዎች እሱን ብቻ የሚፈልጉ ይመስልሃል? አንተም እኔም ጠላቶቻቸው እንደሆንን የሚያስቡ ናቸው፡፡ እጅ መንሻህ ለነሱ ባለህ ፍቅር ተፀንሶ ላላማቸው ባለህ እምነት የተወለደ ገፀ በረከት ሳይሆን፣ ለማምለጥ ከምትፍጨረጨረው ነፍስያህ የመነጨ ደመ ነፍሳዊ ግብዐታቸው መሆኑን ከእኔም ከአንተም በላቀ ሁኔታ አሳምረው ያውቁታል፡፡

ድርቶጋዳን ነው፡፡ ራማቶሓራ ምርምር ላይ! ዣንቶዣራ ደግሞ ጥንታዊውን ታሪክ ሀሰሳ ላይ፡፡ ከሶስቱም አካላት የተውጣጡ፣ በራሳችን የተመረጡ አስራ ሶስት አባላት ያሉት ሴኔት አለ፡፡ አሁን እንደማየው ግን ሁላችንም ወጥተን እየተንጫጫን ነው፡፡ ጊዜ ከመፍጀት በቀር በመንጫጫት ተራራውን የከበበውን ኃይል እንዘነትነውም፡፡ ጉዳዩን ለባለ ጉዳዩ ትተን ወደየስራችን እንመለስ፡፡"

"ይህ እኮ የሞት ሽረት ጉዳይ ነው! ሁላችንንም ያገባናል፡፡ ተራራው ተከቦ ምን ሥራ ይሠራል?" ሲል አንድ ሌላ ሰው ከመሃል ጮሆ ተናገረ፡፡ "እኔ በበኩሌ እንኳዋን ሥራ ልሠራ ይቅርና ሰውነቱ በትክክል መስራቱን እንኳ እጠራጠራለሁ፡፡" ሲል አንድ ሌላ ሰው ከመሃል ጮሆ ተናገረ፡፡

"...ከዚህ ግርግር የሚጠበቅ ነገር አይኖርም፡፡ ስለምን ተኩላ እንደገባበት የበግ መንጋ እንደዚህ እንሸበራለን?"

ሁሉም በአርምሞ ወደየመጣበት ሲመለስ ሚራዥ ደነገጠ፡፡ ትእዛዙ እንደ ጀነራል ትእዛዝ ሲከበር ሲያይ ጫንቃው ላይ ከባድ ሸክም ዘጭ ሲል ተሰማው፡፡ ሻጊዝ ግን ባለበት እንደቆመ ነበር፡፡ ሲጻራም ከሻጊዝ ጎን ቆማ እየተመለከተችው ነበር፡፡ ሆዷ ከበሮ የተሸከመ ደብተራ አስመስሏታል፡፡ ፅንሷ እየገፋ ነው፡፡ በተደረገላት የፅንስ ምርመራ በሆድዋ ያለው ፅንስ ወንድ እንደሆነ ተረጋግጧል፡፡

እንደምንም እየተንገታገተች ሚራዥ ወደ ቆመበት ሄደች፡፡

"እብደሃል?" ስትል ጮኸችበት፡፡ "ስንት የውጊያ መሃንዲሶች እያሉ አንተ ትዕዛዝ ስትሰጥ ትንሽ ሃፍረት አልተሰማህም?"

"እልቅና ከመሬት ወድቆ አይገኝም፡፡ ዝም በማለቱ ስንቱ መሪ በአለቅላቂ ተመርቷል መሰለሽ! .... ሲጻራ.... መደንገጤን ግን አልደብቅሽም፡፡ ደመ ነፍሳዊ ንግግሬን ሰምተው የሚሄዱ አልመሰለኝም፡፡ ታላቅ ሸክም ጭነውኝ ነው የገቡ፡፡ ማወቅ ከፈለግሽ፣ አለቃ መሆን ፈልጌ አይደለም፡፡ አውራ የሌለው ንብ መምሰላችን አስደንግጦኝ ነው፡፡ ይኸው ነው፡፡"

# ፪

## ፍሎሬንስ፥ኢጣሊያ

መስኮቱን ከፍቶ፣ አዲሱን ቀን ወደ ቤቱ ጋበዘው፡፡ ኪራኮስ በሚል ስም የሚታወቀው ይህ ሰው የዶሬቶጋዳ ልዩ ህዋስ የሆነው ዣንቶዣሮ እባል ይሆን ዘንድ ተመልምሎ የነበረው በአባቱ በኩል ነበር፡፡ ሰሞኑን ባልታወቀ ምክንያት አባቱ ተገድለው በመገኘታቸው ያባቱ አስከሬን ከወጣበት ቤት ለመውጣት ድፍረት አጥቷል፡፡ መስኮቱን ከፍቶ ያስገባው አዲስ ቀንም ከወትሮው የተለየ አይደለም፡፡ አባቱን ከቀበረ ወዲህ፣ ሀሳቡን ነፍስ እንደበተነው ነዶ ከሚያዘበራርቁት ተስፋ ቢስ ቀናት የተለየ ቀን እንዳይደለ ያውቃል፡፡ ከቤቱ በታች ጥንታዊቷን ከተማ ፍሎሬንስን ገምሶ ወደ ሚያልፈው የአርኖ ወንዝ በመስኮቱ በኩል ቁልቁል የወረወራቸውን ዓይኖቹን የስልኩ ጥሪ መለሳቸው፡፡ ስልኩ ተመልሶ በቅፅበት ይዘጋበት ይመስል ተስገብግቦ ሮጦ ሲያነሳው፣ ዕርቃኑን እንደነበረ እንኳ ለማስብ ጊዜ አልነበረውም፡፡ ለነገሩ ዕርቃንነቱን የሚያይበት እንደሌለ ገምቷል፡፡ አባቱ ከሞቱ ወዲህ ከዚህ ጣሪያ በታች የሚያየው ዓይን የለም፡፡ አባቱ ለዘመናት በዓለም ዙሪያ ከሰበሰቧቸውና በቤቱ ግድግዳ ዙሪያ ከተደረደሩት መጻህፍት በቀር ማንም የለም፡፡ ይህንን ቤትም ከአባቱ ጣረሞትና ከሌሎች መናፍስት በቀር ማንም ሊጎበኘው እንደማይችል አምኗል፡፡ ልብ አላለም እንጂ እንደተለመደው እርሱ ከሚኖርበት አፓርታማ ፊት ለፊት ካለው ፎቅ፣ በመስኮቱ አትጣጫ መስኮት ያላት አንዲት ሴት ግን ከማዶ አሻግራ እየተመለከተችው ነበር፡፡ የዚህቺን ሴት ማንነት በጊዜ ሂደት ከደረሰበት ቆይቷል፡፡ የእውቁ ስነስብዕ ሊቅ፣ የፕሮፌሰር ዶናዶኒ ኩዊንታና ሴት ልጅ ናት፡፡ ፕሮፌሰሩም የአባቱ ጥብቅ ጓደኛ ከመሆናቸውም በላይ እምና በመኪና አደጋ ከሞተች ኢትዮጵያዊት ሴት፣ ይህችን ቆንጆ እንደሆነች ማንም የሚመሰክርላትን ሊሊያ የተባለች ልጅ፣ እንዲወልዱ ምክንያት የሆኑት አባቱ ባኮስ መሆናቸውን ጠንቅቆ ያውቃል፡፡ እናቷ

ከአባቱ ጋር በሚሠሩት አንድ ረጅም ጊዜ በወሰደ ጥናት ወደዚህ ቤት ሲመላለሱ በፕሮፌሰር ዶናዶኒ እይታ ውስጥ ባይወድቁ ኖሮ ይህቺ አሁን አሻግሬ የምትመለከተው ሴት ወደዚህች ምድር መምጣቷን ይጠራጠራል፡፡

ሊሊያ ዞትር አሻግሬ እንደምትመለከተው ያውቃል፡፡ መኝታ ቤትዋ በሱ መኝታ ቤት ትይዩ በመሆኑ፣ ወደ አልጋዋ ለመውጣት ፒጃማ ስትቀይር ሁሉ ሆን ብላ ትጠብቅና መጋረጃዋን ገልጣ፣ ትራስ መብራትዋን አብርታ፣ እንዲያያት ታደርጋለች፡፡ በነጩ መጋረጃ ውስጥ ጥላዋ እንዲታይ አርጋ ልብሶችዋን ቀስበቀስ ታወልቅና ቀጭን ወገብዋን ሰብቃ ጡቶቿን በጎንዮሽ እንዲያያቸው መጋበዟ የተለመደ ነው፡፡ አሁን አሁን ይህንን ትዕይንት ሳያይ መተኛት ቅርቅር ይለው ጀምሯል፡፡ በአባትዋ ሞያ ተስቦ የስነሰብዕ ተመራማሪ ከሆነ ወዲህ በየምክንያቱ ቤታቸው ሲሄድ ተፋፍረው ዝም መባባላቸው እንጂ ሌላ ጉዳይ ውስጥ የሚያስገባ አጋጣሚ እንኳ አጥተው አልነበረም፡፡ ሊሊያ ኮሪደሩ አካባቢ በተደጋጋሚ እድል እንዲገጥመው ከማመቻቸቷም በተጨማሪ ፕሮፌሰሩ በሌሉበት ሂዶም ብቻዋን አግኝቷት ያውቅ ነበር፡፡ ሆኖም ድፍረቱን ከወዴት እንዳጣው ሳይገባው እስከዛሬ ማዶ ለማዶ በመተያየት ብቻ በሩቅ ቋንቋ ሲነጋገሩ ብዙ ጊዜያት ተቆጥረዋል፡፡ ዛሬ ማን ገና በጠዋቱ የጎደኖችዋ ጨረሮች እንዳረፉበት እንኳ ልብ አላለም፡፡

ኪራኮስ ባነሳው ስልክ ውስጥ የሚሰማውን ነገር ለማመን እንደቸገረው፣ የግንባሩ ቆዳ እሳት እንደነካው ሻማ ጨርቅ መሸብሸብና የቅንድቡ ትዕቢታዊ ቁጥር ፈታ ማለት ያሳብቃሉ፡፡ በዶርቶጋዳ ድርጅት ውስጥ ኮድ 333 የሚል መጠሪያ የተሰጣትና ሜሮዳ የተባለች ሴት ስልኩን ያነሳው ሰው ኪራኮስ መሆኑን ካረጋገጠች በኋላ ነበር ከኢትዮጵያ ደውላ የምታናግረው፡፡

"ቁጥር 333.....ቀጥይ፡፡"

"የምነግርህን ልብ ብለህ አዳምጠኝ፡፡... የምልህን አንድ በአንድ አዳምጠኝ፡፡" ከወዲያኛው ጫፍ በፍጥነት የሚያናግረው ፈጣን የሴት ድምጽ ለአፍታ ጋብ አለ፡፡

"እሺ. ..." ከወዲህኛው ጫፍ እያዳመጠ መሆኑን አረጋገጠ፡፡ የሜሮዳ ድምጽ መሆኑን አልተጠራጠረም፡፡ 333 እጅ ከተቆረጠ ወዲህ የተሰጣት የኮድ ስም መሆኑን ያውቃል፡፡ አዲስ አበባ

ሀዋስ መሪ ዝነኛዋ ሚሮዱ መሆንዋን
ውስጥ የተደራጀውን ሀዋስ መሪ
ለመረዳት ጊዜ አልፈጀበትም፡፡

"እየሰማኸኝ ነው?"

"በትክክል፡፡ 333.... ቀጥይ፡፡"

"በትክክል፡፡ 333.... የሚገኘው ሀዋስ በሰርጎ

"ኢትዮጵያ ውስጥ በተራራው የሚገኘው ሀዋስ በሰርጎ ገቦችና በቅጥረኞች ተጋልጧል፡፡ ተራራውም ተከቧል፡፡ በአንተ መዳፍ የአሜሪካው ሲልም በሲ.አይ.ኤ. እጅ ወድቋል፡፡ በአንተ መዳፍ ላይ ከሚገኘው የአውሮፓው መቀጥር በቀር ሁሉም አደጋ ላይ ነው፡፡ ለጊዜው ሌላ ትዕዛዝ ከእኔ እስከምትቀበል ድረስ ከማንም ጋር ... እደግመዋለሁ፡ ከማንም ጋር በግልዕም ሆነ በህቡዕ እንዳትገናኝ፡፡ መደበኛም ሆነ መደበኛ ያልሆነ ስብሰባ ማድረግ በጥብቅ የተከለከለ ነው፡፡ ከዚህ በኋላ ትዕዛዝ የምትቀበለው ከእኔ ብቻ ሲሆን፡ አንተ ግን ወደ እኔ ደብዳቤ ለመጻፍም ሆነ ስልክ ለመደወል አልተፈቀደልህም፡፡ ከአንተ ሪፖርት ስፈልግ ደውዬ እቀበልሃለሁ፡፡ ራስህን ጠብቅ፡፡ ከራስህም ቢሆን ራስህን ጠብቅ፡፡" ስልኩ ከወዲያኛው ጫፍ በፍጥነት ቢዘጋም የእሱን እጀታ ግን ጆሮው ላይ እንደደቀነ ፈዞ ቀረ፡፡

# ፫

## አዲስ አበባ ፥ ኢትዮጵያ

የጊዜ ሽረሪት ድሩን ያደራበት ግንባራቸውን አሻሽተው እንደገና በግድ ፈገግ አሉ- የእልህ ፈገግታ፡፡ የሚናገሩትን ማንም ሊያዳምጣቸው አልቻለም፡፡ ቅልጥ ባለው ጭፈራ ቤት ውስጥ የሽማግሌውን ንግግር ከጥጋቸው ከተቀመጡት ሁለት ጥንዶች በቀር የሚያዳምጣቸው እንደሌለ ያውቁታል፡፡ የከሳዋው ሽማግሌ መልእክትም ወደነዚህ ጥንዶች ብቻ እንዲደርስ የተፈለገ ይመስላል፡፡ ወደ ሴቷ ተመለከቱ፡፡ የግራ እጇን መቆረጥ የተንጠለጠለው ልፍስፍስ እጅጌዋ ያሳብቃል፡፡ ለዚህ ደንታ እንደሌላት ብቻም ሳይሆን የተሟላ ስነ ልቡና እንዳላት ከሁኔታዋ ተገንዝበዋል፡፡ አብሯት የተቀመጠው ወንድም ወንዳወንድነቱ በግልፅ ያስታውቃል፡፡ ሽማግሌው የሁለቱን ጥንዶች ትኩረት ማግኘታቸውን እንደገና ካረጋገጡ በኋላ በቦታው አስደንጋጭ የሆነ ንግግራቸውን ገፉበት፡፡

"ገዥው አካል የራሱ ፕሮፖጋንዳ ሰልችቶት በማዛጋት ላይ ነው፡፡ ሹማምንቱም በሙስና ተጨማልቀዋል፡፡ ... የተጨማለቀ እጃቸውን ከመታጠብ ይልቅ፣ ወንጀላቸውን ለመደበቅ ስለ ስርዓቱ ዘላለማዊነት እስከደም ጠብታ ይታገላሉ፡፡ ለስርዓቱ አስጊ የሆኑ እጆችን በፍጥነት እስከወዲያኛው እንዲሰበሰቡ ያደርጋሉ፤ አፎችም እንዲገጠሙ ያደርጋሉ፡፡" ሽማግሌው የልብልብ ገዝተው ከተቀመጡበት ብድግ አሉ፡፡ "አስተዳደሩ የትውልዱን ሞራል አላሽቋል፡፡ ምግባረ ብልሹነት እና ክብረ ቢስነት በርክቷል፡፡ የቀቢፀ ተስፋ ቆፈን የብዙሃኑን ልብ አኮማትሮታል፡፡ ልጃገረዶች እንደ በግ እየተነዱ በረሃዎችን በእግር በማቋረጥ ለአረብ ግርድናና እረኝነት ተሸጠዋል፡፡ ገሚሶቹ የአረብ ግመል እረኞች፣ ከፊሎቹም ቴምር ለቃሚዎች ሆነዋል፡፡ ዕድለቢሶቹም የሰውነት ብልቶቻቸው እየወጡ ተቸብችበውባቸዋል፡፡ ብዙዎቹ ልብ፣ ኩላሊትና ጉበታቸው ያለምንም ማደንዘዣ ተወስደውባቸዋል፡፡ በድናቸውም ለበረሀ አሞራ ተጥሏል፡፡ከነዚህ ውስጥ ልጄ አንዷ ናት፡፡" ሽማግሌው ጥቂት አቀርቅረው ቆይተው ዕንባ ካቀረሩ ዓይኖቻቸው ጋር እንደገና ቀና አሉ፡፡

“ትውልዱ ምን ተስፋ አለው? እኔስ እንግዴህ ምን ተስፋ ሊኖረኝ? አንዷ ልጄ እኔን ላለማስጨነቅ ስትሰደድ ለአሞራ ተጥላለች፡፡ ባለቤቴ ጤፍ ከሸመተች ዓመት አልፏታል፡፡ ቤታችን ከጣራው እስከግድግዳው በችጋር ተሞልቷል፡፡ የጠቅላይ ሚኒስትሩ ሥርዓት አልበኛ ጀሌዎች ግን ፍትሐዊ ያልሆነ ግብር በመሰብሰብ ተጠምደዋል፡፡ የልጄ አሞራ የተቃማው ሥጋና አጥንት ግን ምናቸውም አይደለም፡፡ አልሰበሰቡትም፡፡ እነሱን ብትቃወም ኖሮ ግን በረሃና ባህር አቋርጠው አይለቋትም ነበር፡፡ የልጄ እጣ ፈንታ የሀገሪቷ እጣ ፈንታ ነው፡፡ ባይሆንማ እንዲህ ባልሆነች፡፡ አሜሪካዊት ወይ እንግሊዛዊት ብትሆን ኖሮ፣ የልጄን ሥጋ አጋንንት እንደሚቃሟት የተከነነች ነፍስ፣ የበረሃ አሞሮች ባልተቃሟትም ነበር፡፡ ታዲያ ምን ያረጋል!? የዚህች ሀገር ተውሳክ ያበረራት ልጄን ከእንግዲህ አላያትም፡፡ ይህ የእኔ ብቻ ውርደት አይደለም፡፡ ቢገባችሁ የሁላችንም ውርደት ነው፡፡” ሽማግሌው ፊት ለፊት ወዳሉት ቀና ብለው ብሶታቸውን ቀጠሉ፡፡ “ትውልዱ ለምን ይሰደዳል? ፖለቲከኛው የተሸናፊት ስነልቦና ይዞ ስለሚገባ ያንድ ሰሞን ግርግር ፈጥሮ እውቅናን ለማግኘትና በውጭ መንግሥታት በቀላሉ ጥገኝነት የሚያገኝበትን መላ ለመምታት እንጂ፣ ላመኑበት ነገር ህይወታቸውን የሚሰጡ አይደሉም፡፡ እነዚህ ከስደተኞቹ ሳይሆን ከኮብላዮቹ የሚመደቡ ናቸው! ሀገሩ ውስጥ ሰርቶ ለመክበርና ለመከበር ሞክሮ ያቃተው፣ ዙሪያው በቢሮክራሲ ጨለማ የተዋጠበት፣ ለማንኛውም ግልጋሎት እጅ እጁ የታየበት፣ ሰርቶ ለሚያገኘው ንብረት የእርሱ ሁኖ ለመዝለቁ ስጋት ያለበት፣ የጉልበት ብዝበዛውና ገቢው አራምባና ቆቦ ሆኖ የዘወትር ኑሮው እጅላፉ የሆነበት፣ ይህ ቢሰደድ ተሰደደስ ቢባል ማነው ተጠያቂ? ጭላንጭሉን ሁሉ ዘግተውታል፡፡ ከምንቆነጥረው ይቆነጥራሉ፤ ከምንጎነጨው ይጎነጫሉ፤ ቀረጥ የማይቆርጡብን ለምንጎነጨው መከራና ችጋር ብቻ ነው፡፡ ስደታችን አያስደነግጣቸውም፡፡ ሀገሪቷ ከጉሮሮዋ መንጭቃ ያስተማረችው ኃይል እየጎረፈ ነው፡፡ ሀገሪቷ የተማረ ባሪያ ለባዕዳን እየገበረች ነው፡፡ ይህን መገደብ አልቻሉም፡፡ የሰው ኃይሏን መገደብ ዓባይን ከመገደብ ይበልጣል፡፡ ዓባይን በድንጋይ መገደብ ሲቻል፣ ስደተኛን ግን መገደብ የሚቻለው ብዙ የስራ እድል በመፍጠር፣ ሰዎችን በፖለቲካ አመለካከታቸው ባለማግለልና ባለማዳላት፣ ዜጎች

ስርተው ለመብልፀግ እኩል ዕድል ሲኖራቸው ወዙተርፈ ነው!" ሽማግሌው ትንሽ ትንፋሽ ወስደው ቀጠሉ፡፡

"ነገር ግን ሁኔታው የዚህ ተቃራኒ ነው፡፡ ወጣቶች ተመርቀው ሥራ ለማግኘት የተሳትፎ ወረቀት ይጠየቃሉ፡፡ ተሳትፎ ምንድን ነው? ሥራ ለማግኘት የኢህአዴግ የወጣቶች ሊግ አባል መሆን፡ የኢህአዴግ የሴቶች ሊግ አባል መሆን፡ እንዴት ስደት ይነስ? ለዚህ ለዚህማ ደርጉስ እኢወማ፡ እኢሴማ ይል አልነበር እንዴ? መቼ ነው ይህቺ ሀገር ቀን የሚወጣላት? መቼ ነው ተውሳኳ የሚራገፍላት? ለተውሳኮች ስደታችንም ሆነ ስቃያችን ችንፈራችንም ሆነ ችጋራችን ምንማቸውም አይደለም፡፡ የእያንዳንዱን ሰው ህይወት ከጥፍራቸው እድፍ ለማይቆጥሩት ተውሳኮች ይህ ሁሉ ምናቸውም አይደለም፡፡

"የሀገሪቷ ተውሳክ የያንዳንዱ ግለሰብ ተውሳክ መሆኑን ግን እናውቃለን፡፡ ፀረ ተውሳኩን ሁሉም እንደሚፈልግም እናውቃለን፡፡ ፀረ-ተውሳክ! ፀረ-ትንትን! ፀረ- ዱቄንዱቂት! ፀረ-ወሮበላ!... የመድኃኒት ያለሽ!..." ንግግራቸውን ሳይጨርሱ ሁለት የሰማይ ስባሪ የሚያካክሉ ጋርዶች እጅና እጃቸውን ይዘው እየጎተቱ አስወጧቸው፡፡ በቻይናዎች የተሞላውን የጭፍራ ቤቱን ወለል አቋርጠው ሲያልፉ፡ አንገታቸውን ወደ ኋላ ጠምዝዘው የተናገሩት ግን ንግግራቸውን ዳንኪራውና ጩኸቱ ሳይበግራቸው ሲያዳምጡ የቆይቱን ጥንዶች ብቻ ሳይሆን፡ ጋርዶችን ሳይቀር አስፈግጓቸዋል፡፡

"ለነዚህ ቻይናዎች ኢትዮጵያን በጦር ሳይሆን በጡጠ መውረር እንደሚቻል ማነው ያስተማራቸው?....በየተፋጠጥ ቤቱ እየዞሩ ከአረብ በተረፉት ኮረዶቻችን ይጫዎታሉ፡፡ ሀገራቸው ውስጥ እንዲህ መቅበጥ ብርቃቸው የሆነውን ያህል እዚህ በገፍ አግኝተውታል..." ነበር እያሉ የወጡት፡፡ ጥግ ይዘው የተቀመጡት ጥንዶች በፈገግታና በትዝምታ መካከል ባለ ገፅታ ተያዩ፡፡ እነዚህ ሁለት ሰዎች ጌራና ሜሮዳ መሆናቸውን ከነሱ በቀር ማንም እንደማያውቅ ተስፋ አድርገዋል፡፡

"ደርሰውብናል!" ስትል ስጋትዋን ገለጸች- ሜሮዳ ጥቂት ስታምሰለስል ከቆየች በኋላ፡፡ "ማንነታችን አውቀዋል፡፡"

"ምን?!" ጌራ ወደ ሜሮዳ በድንጋጤ አፍጥጦ ጠየቀ፡፡ "ምን ማለትሽ ነው? ... እንዴት ሊሆን ይችላል?!"

"ድርጅቱንና የድርጅቱን አባላት በደንብ የሚያውቅ አባል ሳያጋልጥ አልቀረም፡፡"ሜሮዳ መረበሽዋ እንዳይጋለጥባት

እየተጠንቀቀች ቅድም ያስቀዳችውን ቮድካ ተጎንጭታ ታብራራለት ጀመር፡፡ "ሽማግሌው ይለፈልፉት የነበረው ሁሉ የእኛን አእምሮና ስሜት ከሁኔታችን ለመረዳት የተሰናዳ መሆኑን መረዳት አያዳግትም፡፡ ተላላኪ ሰላይ መሆናቸውን መጠርጠር ተገቢ ነው፡፡"

"ምን ማለትሽ ነው ሜሮዳ!? ይህን የመሰለ ልብ የሚነካና ሰው ሁሉ አፉን ከፍቶ ያዳመጠውን ንግግር ለስለላ ይጠቀሙታል ነው ምትይኝ? ይህማ የማይታመን ነው! ባሉት አሰቃቂ ሁኔታዎች ተስፋ የቆረጡ ነው የሚመስሉት፡፡ ምናልባት የከሰሩ ነጋዴ ሳይሆኑ አይቀሩም፡፡ መንግሥት በያንዳንዱ ቢዝነስ ውስጥ እጁን ማስገባቱ ብቻም ሳይሆን፣ ነጋዴውም እርሱ፣ ቀረጥ ተቀባዩም እርሱ ሆኖ ዜጎች በነፃ መወዳደር ባለመቻላቸው እራሳቸውን ለማጥፋት ገመድና ዛፍ ፈላጊዎች በርክተዋል፡፡ ሰውየው ከነዚህ አንዱ ሊሆኑ ይችላሉ፡፡ ባለፈው አንድ ነጋዴ 'ሊታነቅ ተቃርቤ ነበር፡፡ ገመዱን ከነርሱ ገዝቼ ነበር፡፡ ዛፉን ሁሉ ጣውላ እያደረጉ ውጭ ሀገር ስለሸጡት መንጠልጠያ ዛፍ አጥቼ ተውኩት፡፡' ሲሉ ነበር የምሬታቸውን ጫፍ የነገሩኝ፡፡ ያሁኑ ሽማግሌም….."

"የተናገሩት ነገር ትክክል ነው፣ ሰህ አይወጣለትም፡፡ ይህ ንግግራቸው ግን ስሜታዊ ሊያረግ የሚችልና በትክክል ለኛ ተብሎ የተዘጋጀ ነው፡፡ ሰውየው ካላጡት ቦታ እኛ አጠገብ መጥተው በመቀመጥ የእኛን ስሜት በውል ለማንበብ በሚያስችል ቅርበት ነበር ይናገሩ የነበሩት፡፡ ካለኝ ልምድ በመነሳት ጥርጣሬዬ ሁሉ እውነት መሆኑን ትረዳለህ፡፡ ይህን ዓይነት ንግግር በየካቲካላ ቤቱና ህዝብ በተሰበሰበት የሚናገሩ ሰዎች 'አስተንፋሾች' ተብለው ይጠራሉ፡፡ የህዝቡን ውስጣዊ ስሜት እና ያበጠን ልብ በንግግር ለማስተንፈስ መንግሥት የሚቀጥራቸው ናቸው፡፡ አንዳንድ ቅጥረኛ የፖለቲካ ፓርቲዎችና ጋዜጠኞችም የማስተንፈሱ ሥራ የተሰጣቸው ናቸው፡፡ የህዝቡን የልብ ትርታ በመናገር ያበጠ ልቡን ያስተነፍሱታል፡፡ ጩኸቴ ከተሰማልኝ ምን ቀረኝ የሚለው የሰፊው ህዝብ ሰፊ ሆድ ለጊዜው እንደተነፈሰ ከበሮ ይረግባል፡፡ ጥያቄው የተመለሰለት ይመስለዋል፡፡ …"

"ሜሮዳ … ይልቅስ ማብራሪያውን ተይውና እንዴት እርገን ከዚህ ወጥመድ እንደምንወጣ እንዘጋጅ፡፡ 'ያልጠረጠረ ተመነጠረ' ይላሉ አበው!" ጌራ በደመ ነፍስ ተቁነጠነጠ፡፡

"ለጊዜው ያሰብኩት ነገር የለም፡፡ ይኸኔ እዚህ ጭፈራ ቤት ካሉት ሰዎች ውስጥ የእኛን ሁኔታ የሚከታተሉ ሰዎች ይኖራሉ፡፡ ከውጭ ደግሞ የታጠቁ ሰዎች እስክንወጣ እየጠበቁን ይሆናል፡፡"

"ታዲያ ምን ተሻለን?"

"ሰከን በል፡፡ አትቁነጥነጥ!" ሚርዳ ቮድካዋን ደጋግማ ተጎነጨች፡፡

# ፬

## ፍሎረንስ፣ ኢጣሊያ

ዕርቃኑን መሆኑን ያሳየው የቆመ መስታወት ነበር፡፡ 'ከገነት የተባረረውን አዳም መስያለሁ፡፡' ሲል ለራሱ ተናገረ- ኪራኮስ፡፡ መለስና አዳም ከገነት የተባረረው ባባረረው ፈጣሪ የቆዳ ልብስ ተውቦ እንደነበር አስታውሶ ፈገግ በማለት 'በትጣት መሀል ያለ ምህረት' አለ በልቡ፡፡'አዳምስ የተባረረው ትጠሏን በመቅመስና የቆዳ ልብስ በመልበስ ነው፡፡ ክብርን ተገፎ እርቃንን ከሀገር መባረርስ ምን ይባላል?'

ወደ ጠይም ምስሉ አንድ እርምጃ ሲቀርብ ምስሉም አንድ እርምጃ ቀረበው፡፡ ሁለት እርምጃ ሲጠጋ ምስሉም ሁለት እርምጃ ተጠጋው፡፡

'ራስን ፍለጋ' የሚል ሀሳብ ብልጭ አለለት፡፡ 'የጠፋውን ማንነት ፍለጋ፡፡' ይህን ሀሳብ እንዲያመነኝርግ ያስገደደው የስነሰብዕ ተመራማሪነቱ ብቻ እንዳይደለ ያውቃል፤ የዣንቶዣራ ኃላፊነቱም ጭምር እንጂ፡፡

በእውቁ ፍሎረንስ ዩኒቨርስቲ የአንትሮፖሎጂ መምህር ሆኖ ከተቀጠረ ወዲህ ብቻም ሳይሆን ዣንቶዣራ ከሆነ ወዲህ ራሱን መንከባከቡን ችላ ማለቱን ከፊት ለፊቱ የቆመ ምስሉ ባልተበጠረ ዝብርቅርቅ ፀጉሩ እና ባልተላጨ ጢሙ እያሳየውም፣ አእምሮው ግን "ራስን ፍለጋ" በሚለው ሀሳብ ላይ እንደ ችካል ተቀብቅቦ አልነቀል አለው፡፡

ይበልጥ ወደ መስታወቱ ተጠግቶ ግንባሩን ከምስሉ ግንባር፡ አላጥቆ "ራስን ፍለጋ... የጠፋውን ማንነት ፍለጋ... ግልቡን ስልጣኔ መግለብ..." እያለ ብቻውን መልስ ከማይሰጠው መስታወት ጋር ይነጋገር ጀመር፡፡ ትኩሱ የማለዳ ትንፋሹ ያረፈበት የመስታወቱ ገጽ ደብዝዞ መልኩን ሰወረበት፡፡ የግዱን ፈገግ አለ፡፡ መስታወቱ በቅኔ የመለሰለት መሰለው፡፡

"በገዛ ትንፋሽ ውስጥ መደበቅ! በገዛ አእምሮ ውስጥ መደበቅ! በገዛ ሀገር ውስጥ መደበቅ!..." ፈገግ ብሎ በገዛ ትንፋሹ

እንፋሎት ደብዝዞ መልኩን የሰወረበትን መስታወት በመዳፉ ሞገርቀው፡፡ ዓይኖቹን ተመለከታቸው፡፡ ጥርት ያሉት ዓይኖቹ አልዋሹትም፡፡ እምርሮ ራሱን እየፈለገ መሆኑን ነገሩት፡፡

"ርቆ የተቀበረ ማንነትን ፍለጋ!" በሲረኞች በየሥርቻው የተደበቀ ማንነትን ፍለጋ ..." አሁንም መስታውቱ ደበዘዘ፡፡ ላቦቱ ያደበዘዘውን መስታውት እንደገና ሞዠርቆ፣ ፀጉሩን ያበጥር ጀመር፡፡ አፍሮ ጎፈሬውን ክፍክፎ ጠይም ፊቱን በተገቢባው ውሃ አለቀለቀው፡፡ ጥርሱን ቦርሾ ምስቅልቅሉን ሁሉ አብሮ ይተፋው ይመስል ጉምጥምጡን በኃይል ተፍቶ በፍጥነት ይለባብስ ጀመር፡፡ እንደ ተለመደው ጥቁር ሱፉን እንደገጠመ ከለበሰ በኋላ ባለረጅም ኮሌታ ነጭ ሸሚዙን እያስተካከለ ወደ ቁሙ መስታወት ተመለሰ፡፡

እንዳማረበት ወይም እንዳላማረበት ለማየት ይሁን ወይም አይሁን ሳያውቀው፡፡ የራሱን ምስል ከመስታውቱ ፊት ለፊት ተገትሮ አገኘው፡፡ የቅድሙ ርቃን ምስሉ አይደለም፡፡ ጥቁር ሱፍና ባለረጅም ኮሌታ ነጭ ሸሚዝ የለበሰ የስልሳዎቹንና የሰባዎቹን ኢትዮጵያውያን ዘመን ፋሽን ተጋሪ የመሰለ ጎልማሳ፡፡ የአህያ ጆሮ የሚያክል ኮሌታ ያለው ነጭ ሸሚዝ፣ ምናልባት ቢተረተር ቀሚስ (እትንኩኝ) ሊሆን የሚችል ጭን ጠባብ፣ እግረ ሰፊ ቦላሌ የሰደደ የራሱ ምስል፡፡ ጎፈሬውን ክፍክፎ አርበኛ መስሎ የቆመ ጅንን አፍሪካዊ፡፡

አዛውንቱ አባቱ፣ ከሞቱ ወዲህ የልቡን የሚያወራው ይኸው የራሱ ምስል ብቻ ነው፡፡ ከፈረንጅ ጋር ለስራ ጉዳይ ካልሆነ በቀር የሆዱን አውርቶ አያውቅም፡፡ አባቱ ወደ ፍሎረንስ ካመጡት ዓመታትን ቢያስቆጥርም እዚህ ግባ የሚባል ጓደኛ አላፈራም፡፡ ወደ ጓደኛው ተመለከተ - ወደ ራሱ ምስል፡፡ አባቱም ከልጅነቱ ጀምረው 'ራስህን ተመልከት፣ ራስህን መርምር፣ ጀርባህን ተመልከት...' ማለት ልማዳቸው ነበር፡፡' መልኩንም ሆነ ራሱን በመመልከቱ ውስጥ ያባቱ ተፅዕኖ ሳይኖርበት አይቀርም፡፡ በልጅነቱ መልኩን በጉልምስናው ውስጡን መመልከት ልማዱ ሆኖ ቀርቷል፡፡ ለእርሱ፣ መስታወት መልክን ብቻ መመልከቻ ተራ ጠርሙስ ሳይሆን፣ ራስን መመርመሪያ አጉሊ መነፅርም ጭምር ነው፡፡

ትወደዋለህ? በእርግጥ ራስ

'በእርግጥ ራስህን ብታገኘው የምትለው የትኛውን ማለት ምን ማለት ነው? ኢትዮጵያዊነት የምትለው የትኛውን ኢትዮጵያዊነት ነው? የጠፋው ስልጣኔ የምትለውስ የትኛውን ነው? ልብስህ ስልጣኔ ነው? ግልቡ ስልጣኔ የምትለውስ የትኛውን ነው? የተወጠቀው በአውሮጳ የአውሮጳ! እውቀትህ የአውሮጳ! ክርስህ የተወጠቀው በአውሮጳ ምግብ! ምንህ ነው ኢትዮጵያዊ? ቆዳህ? ... እኒያ ባተሌ አባትህ ዕድሜ ልካቸውን ባዝነው ምን ጠብ የሚል ነገር አገኙ? ...' የገዛ

ምስሉ በጥያቄ ያጣድፈው ጀመር፡፡

'ልትላቂ ጠጥቼ ልብሴ የሰው አጻፋ፣
በሰው ምዕዋት ሳልወቀስ በሰው ውራጅ ሳልከረፋ፣
ከነክብሬ ተቀብሬ ምነው ስሜ በጠፋ!'

በጀርመን ድምፅ ዘውዱ ታደሰ በሚባል እውቅ ጋዜጠኛ "ላሚቦራ" የተሰኘው እንቆርቋሪነት ከዓመታት በፊት የሰማውና የየኛው ተሰማ ግጥም የእንጉርጉሮው አካል ሆነ፡፡

ህይወትና በቅርብ

'እኛ ኢትዮጵያውያን ለምን በምንኖረው ሥርአቶች ደስተኛ አልሆንም? ጊዜያት ተፈራርቀው በገዙን ምክንያቱም ታላቅ ስለነበርን ታናሽ ሆነን ለመኖር አሜን ማለት ስላቃተን ነው፤ የዕውቀትና የስልጣኔ' መሠረት እንዳልነበርን የማንም ውዳቂ ርዕዮተ አለምና ሳልባጅ መራገፊያ ስለሆንን ነው፤ ዓለምን ከባርነት ነፃ ለማውጣት እንዳልታገልን ዛሬ የጥንት ጠላቶቻችን ባርያ ስለሆንን ነው፡፡' የበሩ መንኳኳት ከህሳቡ አናጥቦ ምስሉ ላይ የተቸናከሩ ዓይኖቹን ነቀላቸው፡፡

ወደ በሩ በዝግታ ተራምዶ በማጮለቂያው ተመለከተ፡፡

ሊሊያ መሆንዋን አጮልቆ ሲያይ አረጋገጠ፡፡የታዋቂው የስነሰብዕ ተመራማሪ የፕሮፌሰር ዶናዶኒ ኩዊንታና ልጅ ሊሊያ፡፡ 'እሻግሮ ማየቱ መሯት ቁርጡን ልትነግረኝ ይሆን ወይስ በሌላ ምክንያት ስተት ብላ ቤቴ ድረስ የመጣችው?' እየተወዛገበ በሩን ከፈተ፡፡

# ፫

## አዲስ አበባ ፣ ኢትዮጵያ

አንድ ማንነቱ ያልታወቀ ግለሰብ ወደ ኢትዮጵያ ብሔራዊ ደህንነትና መረጃ አገልግሎት ቢሮ ስልክ ደውሎ ነበር፡፡

"ጊዜ የለኝም!" ሲል ነበር ሰላምታ ያላስቀደመ ንግግሩን በወፍራም ድምፁ የጀመረው፡፡ "እጅግ ወደር የማይገኝለት መረጃ አለኝ፡፡ ምን ያህል ትከፍሉኛላችሁ?"

ይህንን ስልክ የተቀበለው ሰው በብሔራዊ የደህንነትና የመረጃ አገልግሎት ቢሮ ውስጥ በተቀመጠበት ተቁነጠነጠ፡፡ ነገር ግን ጠና ያለው ሰውዬ መጓጓቱ እንዳያስታውቅበት ተጠነቀቀ፡፡

"ማን ልበል ጌታዬ?"

"ሃ ሃ ሃ ..." መረጃ ሻጩ ሰውዬ ከወዲያኛው ጫፍ ተሳለቀ፡፡ የደህንነት ቢሮው ባልደረባ ግን ስልኩ እስኪጠለፍ ጊዜ እየሸመተ ነበር፡፡ መረጃ አለኝ ባዩ ሲደውል ይህ ለሁለተኛ ጊዜ ነበር፡፡ የሚያናግረው የደህንነት ቢሮ አባልም በጥንቃቄ የተመረጠና አጥምዶ በመያዝ ወደር የለውም የሚባልለት ነው፡፡ ይህም ሰው በቁልምጫ ስሙ ቀንጠፋው ይባላል፡፡

በመጀመሪያው ቀን ለደዋይ የተመለሰለት መልስ "ተሳስተዋል" የሚል ነበር፡፡ ቀጠን ያለውና እንደሙለታ የሚጎረፈው የሴት ድምጽ "ተሳስተዋል ጌታዬ! የመረጃ አገልግሎት ቢሮ ስልክ አይደለም!" ሲል ነበር የመለሰለት፡፡ የደወለበት ስልክ ቋሚ የህዝብ ስልክ በመሆኑ የየት ክልል ስልክ እንደሆነ፣ ከተማውንም በተለይም፣ አካባቢውን ለመለየት ሙከራ ተደረገ፡፡ ነገር ግን ወዲያው ነበር ደዋዩ ስልኩን የጠረቀመው፡፡ ከአራት ቀናት በኋላ ግን ይኸው እንደገና ደወለ፡፡ ቀንጠፋውም የዚህን ሰውዬ ስልክ በመጠበቅ ተጠምዶ ነበር፡፡ ስልኩን አንስቶ የሚያናገረው ማን መሆኑን ቢያውቅ ኖሮ እንደገና ባልደወለም ነበር፡፡ ይልቁንስ የሚደበቅበት ጉሽጉሻ በፈለገ ነበር፡፡

# ፯

## አዲስ አበባ ፣ ኢትዮጵያ

"መልኳን እንደራሴ መልክ አውቀዋለሁ፡፡ በተገነጠለው ገስ ኦፕሬሽን ጊዜ በጠና በመመታቱ ተቆርጧል፡፡ ግራ እጁ ቆማጣ ነው፡፡ ነገር ግን የግራ እጁ መቆረጥ እጁ ቀኝ እጁም ጭምር ቢቆረጥ እሷ ምላጭ መሳቢያ እንዳልያዘችኝም ይገርመኛል፡፡" በቀንጠፋው የፀና ምርመራ ውስጥ የሚገኘው አፈንጋጩ አማዲዎ የተናገራቸው ቃላት ነበሩ፡፡ቀንጠፋው ግን ይህንን አፈንጋጭ በቀላሉ ሊያምነው አልቻለም፡፡ ሆን ተብሎ እጅ እንዲሰጥ የተደረገ ሰው ነው በሚል ተጠራጥሮታል፡፡ ለምን ማፈንገጥ እንደፈለገ ሲጠየቅ፡ ቀንጠፋውን የማያጠግብ መልስ ነበር የመለሰለት፡፡ መልሱም "የራሴን ኑሮ መኖር እፈልጋለሁ፡፡ እነሱ ግን ሊለቁኝ አልቻሉም፡፡ ካልጠፉ ደግሞ መኖር አልችልም፡፡ ወደ ድርጅቱ መግባት እንጂ መውጣት አይቻልም፡፡" ቀንጠፋው ግን በዚህ ሊለቀው አልፈለገም፡፡ ቆሻሻ ወደሞላበት በርሜል አንገቱን እያስጠለቀ ቀን ከሌት ይነዘንዘው ገባ፡፡

"እባካችሁ ..." ሲጠናበት ያልጠየቁትን ሁሉ ይቀባጥር ጀመር፡፡ "እባካችሁ ...ተራራውን አሳያችኋለሁ፡፡ ሜሮዳንም አሳያችኋለሁ፡፡ የዴርቶጋዳ አባላትን ሙሉ በሙሉ ጉንጫቸውን በጣቴ እየጠቆምኩ አሳያችኋለሁ፡፡ ሁሉንም መልካቸውን እንደራሴ መልክ አውቀዋለሁ፡፡ እባካችሁ ..."
በቅጽል ስሙ አማዲዎ እየተባለ የሚጠራው ይህ አፈንጋጭ ሰው ያልቀባጠረው ነገር አልነበረም፡፡ የሚያሸክተውን ሁሉ ችላ ያሉ መስለው በደንብ መዘበሩት፡፡ አማዲዎ በአእምሮው የመዘገበውንና ሊሸጠው ያሰበውን መረጃ ያወጣው ከዚሁ አሰቃቂ ምርመራ በኋላ ነው፡፡ ኢንጂነር ሻጊዝ በተራራው ውስጥ መኖሩን ሳይቀር ለፈለፈ፡፡ ከዚህ ሁሉ በኋላ ነበር ቀንጠፋው በበኩሉ የአማዲዎን ወደር የለሽ መረጃ ለሲ.አይ.ኤዎች ለመሸጥ

የመሰነው፡፡ በመሆኑም ሮበርት ጋሎ በሚባል የሲ.አይ.ኤ ቅጥረኛ የሚመራው ቡድን ኢንጂነሩንና የያዘውን ሳጥን ይዞ ለመሄድ አዲስ አበባ ከገባ ሰንበቷል፡፡ በሮበርት ጋሎ የሚመራው አፋኝ ቡድን የተሰረቀ ሂሳውን ቆርጦ ኢትዮጵያን በማሰስ ላይ ነው፡፡ ቀንጠፋውም ከሲ.አይ.ኤው ቅጥረኛ ኪሱን ሞቅ የሚያደርግ ቀብድ አግኝቷል፡፡ ቀሪውና ዋናው ጉርሻ ግን ኢንጂነሩ እስከ ሳጥኑ ሲያዝ ብቻ የሚገኝ ይሆናል፡፡ አሁን በማውጠንጠን ላይ የሚገኘውም ይህንኑ ነው፡፡ ኢንጂነሩንና ሳጥኑን በህይወት መያዝ ይሀ ግን የግሉ ምስጢር ብቻ ነው፡፡ ቀንጠፋው በአንድ ድንጋይ ሁለት ወፍ የመምታት እቅዱን በጥንቃቄ ይወጣ ዘንድ በዚህ የመጨረሻ ባለው ምሽት በአንድ ሰፊ ክፍል ውስጥ ብቻውን ታስሮ ወደ ሚቁለጨለጨው እስረኛ አመራ፡፡

ሰፊው ክፍል ቤት ከመሃል ወለሉ ላይ ካለው ብቸኛ ጠረጴዛ ጎን ካሉ ሁለት ወንበሮች በቀር ምንም ሌላ ነገር የለበትም፡፡ እስረኛው ራሱን እንዳያጠፋ ከፍተኛ ጥንቃቄ ተደርጓል፡፡ ራስን ለማጥፋት የሚያስችሉ ቁሳቁሶች ሁሉ በዚህ ቤት ውስጥ እንዳይኖሩ ተደርገዋል፡፡ ቀንጠፋው ሲጋራውን በቀስታ እየማገ አማዲዮ ወደ ተቀመጠበት አመራ፡፡ ወንበሩን ስቦ ከፊት ለፊቱ በቀስታ ተቀመጠ፡፡ ሲጋራውን ሁለት ጊዜ ከማገ በኋላ አንድ ቢጫ ወረቀትና አንድ ብዕር ጠረጴዛው ላይ አስቀመጠ፡፡ በዚህ ጊዜ ሁለት ደህንነቶች ወደ አዳራሹ ገቡና ከውስጥ በሩን ቆልፈው ከእስረኛው ኋላ መሳሪያቸውን አቀባብለው ቆሙ፡፡ አንደኛው ከኪሱ የእስረኛውን እጅሙቅ መፍቻ ቁልፍ አውጥቶ የአማዲዮን እጆች ነፃ አወጣቸው፡፡ ቀንጠፋው ከንፈሮቹን በዝግታ አላቆ ዓይኖቹን ወደ ቢጫው ወረቀትና ወደ ብዕሩ ወረወረና እንደገና አማዲዮን ተመለከተው፡፡

"በዚህ ወረቀት ላይ የዴርቶጋዳ አባላትን በሙሉ ስማቸውን ዘርዝርልኝ፡፡"

"ወረቀቱ አይበቃኝም፡፡ ብዙ ናቸው፡፡ እጅግ በጣም ብዙ ...."

"አትጨነቅ የወረቀት ችግር የለብንም፡፡ ይጨመርልሃል፡፡" ቀንጠፋው አቋረጠው፡፡

አማዲዮ ወረቀቱንና ብዕሩን አፈራርቆ ሲመለከት ከኋላው የቆሙት ሁለት ደህንነቶች በድንጋጤ እርስ በእርስ ተያዩ፡፡ የሁለቱን ደህንነቶች መደናገጥ ያልተመለከተው ቀንጣፋው

በዝግታ ተነስቶ አዳራሹን ለቆ እየወጣ እያለ አንድ ጥያቄ
አስከተለ፡፡ ፊቱን ሳያዞር፡፡
"ስንት ወረቀት ያስፈልግሃል?"
"አንድ ደርዘን!" አማዲዎ በዝግታ ተናገረ፡፡
"ሃ ሃ ሃ ... አንድ ደርዘን?!........ አንድ ደርዘን!" ቀንጠፋው
መልሶ በምፀት አንሾካሾከ፡፡
"አንድ ጨምርበት!"አለ አማዲዎ የምስጢሩን ዋጋ ከፍ
ለማድረግም ይሁን ወይም በድንጋጤው ንረት ምክንያት አልያ
እስካሁን ሰው የማይችለውን ሁሉ የቻለበት ስቃይ እንዳይመለስ?
"ለምን?" ቀንጠፋው ፊቱን ሳያዞር ጠየቀው፡፡
"ለምን? ለምን? እ....እ...አስራ ሦስት እንዲሆን ነው፡፡"
"አሥራ ሦስት ምንድን ነው?"
"ምንም! ምንም!....እ...እ... የድርጅቱ አመራሮች ቁጥርና
የምክር ቤቱ መቀመጫ ወንበሮች ቁጥር...."

ሁለቱ ደህንነቶች በድንጋጤ እንደገና ተያዩ፡፡

በዝግታ ተነስቶ አዳራሹን ለቆ እየወጣ እያለ አንድ ጥያቄ አስከተለ፡፡ ፊቱን ሳያዞር፡፡
"ስንት ወረቀት ያስፈልግሃል?"
"አንድ ደርዘን!" አማዲዎ በዝግታ ተናገረ፡፡
"ሃ ሃ ሃ ... አንድ ደርዘን?!........ አንድ ደርዘን!" ቀንጠፋው መልሶ በምፀት እንሾካሾከ፡፡
"አንድ ጨምርበት!"አለ አማዲዎ የምስጢሩን ዋጋ ከፍ ለማድረግም ይሁን ወይም በድንጋጤው ንረት ምክንያት እልያ እስካሁን ሰው የማይችለውን ሁሉ የቻለበት ስቃይ እንዳይመለስ?
"ለምን?" ቀንጠፋው ፊቱን ሳያዞር ጠየቀው፡፡
"ለምን? ለምን? እ....እ...አስራ ሦስት እንዲሆን ነው፡፡"
"አሥራ ሦስት ምንድን ነው?"
"ምንም! ምንም!....እ...እ... የድርጅቱ አመራሮች ቁጥርና የምክር ቤቱ መቀመጫ ወንበሮች ቁጥር...."

ሁለቱ ደህንነቶች በድንጋጤ እንደገና ተያዩ፡፡

በመልክ እያውቁትም፡፡ አሳምራ ሰውየውን በስም እንጂ ሴትዮ ናት፡፡ ሲመጣ በምልክት ታውቀዋለች የተባለችው ራሳቸው ወጥመድ ውስጥ እንደምትነግራቸው ሲጠብቁ በጠና ተጠራጥረዋል፡፡ ገብተዋል፡፡ ሊከበቡ እንደሚችሉ በጠና ተጠራጥረዋል፡፡ ጌራ ግራ ተጋብቶ ሚሮዳን ጠየቃት፡፡

"ምን ይሻላል?" ጌራ ግራ ተጋብቶ ሚሮዳን ጠየቃት፡፡

"ዝም ብለን እንውጣ?"

"አብደሃል?!"...ሚሮዳ ... በዓይኖቿ አስጠነቀቀችው፡፡

"ከውጪ ይይዙናል፡፡"

"ታዲያ ... እዚሁ ...እንደር እንዴ?"

"ሂድና ሴቲቷን የምትተዋወቅ መስለህ አናግራት ... እኔን አመናጭቀኸኝ ሂድ! ...ተነስ!"

"ምን አቅደሽ ነው?"

"ስማኝ! ዝም ብለህ ያልተስማማሁህ መስለህ አመናጭቀኸኝ ሂድ! ቀጥሎ ያለውን ለእኔ ብቻ ተውልኝ፡፡ ያልተስማማሁህ አስመስለህ ሂድ!"

ጌራ ትዕዛዟን ተቀበለ፡፡ እያመናጨቃት በዳንስ ወለሉ ላይ የሚደነክሩትን ተቀላቀለ፡፡

"ይህች 'ማትረባ! ሸርሙጣ! እኔን ከጎኗ አስቀምጣ ዓይኗ ይቃብዛል እንዴ?!" እንዲያውም እርሷን ለማብሸቅ በሚያስመስል መልኩ በቁንጥ እየደነሰ ብቻዋን ወደ ቆመችው ሴትኛ አዳሪ ሄዶ እጇን ሳብ አድርጎ ወደ ዳንስ ወለሉ ወሰዳት፡፡

አንድ ሙዚቃ እስኪያልቅ ድረስ ምንም አላናገራትም፡፡

"ጠጥተሻል እንዴ?!" ሲል ጠየቃት ልጅቷን ጌራ፡፡

"ሁለት ቢራ ጠጥቻለሁ፡፡ ቻይናዎች ሊያስቀምጡኝ አልቻሉም፡፡ አንዱን ሳባርር ሌላው ዕድሉን ለመሞከር ይመጣል፡፡"

"የማትሰክሪ ከሆነ አንድ ሌላ ቢራ ጨምሪበት፡፡" ወንዱ አስተናጋጅ ወዲያውኑ ለሁለቱም ቢራ አመጣላቸው፡፡

በዚሁ ቅጽበት አንድ ሰው ሚሮዳ ወደተቀመጠችበት መጥቶ "ቆንጆ ይቅርታ! ሰው ጋር ነሽ?" ሲል ጠየቀ፡፡

"ነበርኩ፡፡" አለችው ሚሮዳ በደረቁ ፈገግ ብላ፡፡ "ጥሎኝ ሄደ ባክህ ..."

"አንቺን የመሰለች ቆንጆማ ብቻዋን እንኳን ይዞን ያዘል
ለአንድ ደቂቃ እንኳ ብቻዋን መቀመጥ የለባትም ነበር፡፡"
"ምን ታረገዋለህ ወንዶች ስትባሉ ..."
"ልቀመጥ ይሆን ታዲያ?"
"ጥለሽኝ እስክትሄድ ተቀመጥ፤ ለጊዜው ብቻዬን ነኝ፡፡"
"ምን ዓይነት ሞኝ ሰው ነው ባክሽ! ... አንዳንድ ወንድ እኮ ውበትን የሚያደበት ዓይነ ይታወርበታል፡፡ እንደ'ቴ አንቺን የመሰለች ቆንጆ ጥሎ ይሄዳል! ..."
"ለዚህ ... ነዋ! ..." ሜሮዳ የተቆረጠ ግራ እጇን አሳየችው፡፡ ፊቱን በውል ተመለከተችው፡፡
የሰውየው ፊት ከየአቅጣጫው ተሸበሸበ፡፡ የተንጠለጠለ እጅጌዋንና ፊቷን አፈራርቆ ተመለከተ፡፡ ሜሮዳ ሰውዬው እንስን ለማንት የገባ መሆን አለመሆኑን ለመረዳት ጣረች፡፡
ሰውየው "ፎራሽ የማያውቃት መሰለ፡፡ እርሷ በእርግጥ ይህን ሰው ከዚህ በፊት አታውቀውም፡፡
"ምንው?!" ሲል እየተናነጋጀ ያመጣለትን ደብል ብላክ ሌብል ውስኪ ተጎንጭቶ እጇን ባገጩ ጠቁሞ ጠየቃት፡፡
"የመኪና አደጋ ነው" አለችው በአጭሩ፡፡
"ውይ! እኔን! እኔን!..." ብሎ ዝም አላት፡፡
በዚሁ ቅጽበት የሜሮዳ ተንቀሳቃሽ ስልክ ጠራ፡፡

ቁጥሩን ተመለከተች፡፡ የዳግማዊ ስልክ ቁጥር ነው፡፡ ዳግማዊ በኢትዮጵያ የደህንነት መስሪያ ቤት ውስጥ ስርጎ እንዲገባ የተደረገና በመጨረሻው ሰዓት ታዲዎስ ኢያሱን አንቀ ተራራው ውስጥ ያሰረ አባል ነው፡፡ ሜሮዳ ተስፈንጥራ ተነስታ ወደ ሽንት ቤቱ ኮሪደር አመራች፡፡
"333 ... አማዲዎ የሁሉንም አባላት ስም በመመዝገብ ላይ ነው፡፡ የእኔ ሰዎች ከጀርባው ቆመው ይህን ጉድ እየተመለከቱ ነው፡፡ እስካሁን ዋና ዋና አባላትን መዝግቧል፡፡ እኔም ሆንኩ የእኔ ሰዎች ከዚህ በኋላ የራሳችን ስም እስኪመዘገብ ቆመን እናየውም፡፡" ስልኩ ተዘጋ፡፡ ሜሮዳ የዳግማዊን ስልክ እንደገና ሞከረች፡፡ ተዘግቷል፡፡ ደንገዝ ጥቂት ከቆመች በኋላ ሽንት ቤቱ ውስጥ ገብታ ተቀመጠች፡፡

ሽንቷን ለመሽናት አማጠች፡፡ አልቻለችም፡፡ ነገር ግን ፊኛዋ እያስጨነቃት ነው፡፡ እንደገና ሞከረች አልቻለችም፡፡ በብስጭት ሱሪዋን ታጥቃ ወደ ነበረችበት ወንበር ተመለሰች፡፡

ዳግማዊ በደህንነት መስሪያ ቤቱ ሲሰርግ፣ መረጃ ከማቀበል ባለፈ በማንኛውም እንቅስቃሴ እንዳይሳተፍ ጥብቅ መመሪያ ተሰጥቶት ነበር፡፡ ይህም የሆነበት ምክንያት በደህንነት መስሪያ ቤቱ ውስጥ እንደገና ሌላ ሰው ለማስረግ አያሌ ጊዜያትን የሚፈጅ ጉዳይ በመሆኑ ነው፡፡

ሜሮዳን ብርክ ያስያዛት ጉዳይም ይኸው ነው፡፡ አማዲዎን ካስወገደው፣ የደህንነት መስሪያ ቤቱ ዳግማዊን ብቻ ሳይሆን ሌሎቹን ሰርጎገቦች ላለመመንጠሩ ማንም እርግጠኛ አይሆንም፡፡ የደህንነት መስሪያ ቤቱ መረጃ ከተቋረጠ ደግሞ በዴርቶጋዳ ላይ የሚወሰነው ውሳኔም ሆነ የሚጠነሰሰው ሴራ ሊታወቅ አይችልም፡፡ የአማዲዎ አፈንጋጭነትም ሆነ ምስጢር ማጋለጥ የተደረሰበት በዳግማዊ በኩል በተዘረጋው ሰንሰለት ነው፡፡ ይህ ሰንሰለት ከተቆረጠ ደግሞ ዴርቶጋዳዎች አስቸጋሪ ሁኔታ ውስጥ እንደሚገቡ የሚያነጋግር ጉዳይ አይደለም፡፡ በዚህ አጣብቂኝ ውስጥ የገባችው ሜሮዳ ይህ ሰንሰለት እንዳይቋረጥ ማድረግ የመጀመሪያ ሥራዋ አድርጋ ከወሰደችው ቆይታለች፡፡ በመሆኑም አማዲዎን የሚያስወግድ ሌላ ቅጥረኛ እንደሚያስፈልጋት አሁን የራሷ ህይወት አጣብቂኝ ውስጥ ገብቶም ማሰላሰሏን አላቆመችም፡፡

ሜሮዳ ወደ ሽንት ቤት ሄዳ በተመለሰችበት ቅፅበት ሰውየው ተንቀሳቃሽ ስልኩን በመነካካት ላይ እያለ ነበር የደረሰችው፡፡

"ተጫወቺ እንጂ! ምነው ጥሎሽ የሄደው ወንድ ይህን ያህል ስሜትሽን ረብሾታል እንዴ?" አላት መጤው ሰውዬ ብላክ ሌብሉን ተጎንጭቶ፡፡ ሲጋራውን እንደገና ለኩሶ ሲያበቃ "ስልክሽ ላይ እኮ ተኛሽበት፡፡" በማለት ተመለከታት፡፡

"በጣም ነው ያናደደኝ! ለምን መሰለህ ..." ሜሮዳ የምትጠጣውን መጠጥ ለመቀየር አሰበች፡፡ ብርጭቆዋ ገና ያልተጋመሰ ቢሆንም ጥላው የሄደችውን መጠጥ እንደገና ተጎንጭታ አታውቅም፡፡

"ለምን መሰለህ ... በወንድ እንዲህ ተንቄ አላውቅም፡፡ "እየህ ግራ እጄን የቆረጥኩት ለጌጥ እይደለም፡፡ እንዲያስጠላብኝም አልነበረም፡፡ ደግሞም ... እንዲህ ቀኝ እጄ ወንዶችን ለማቀፍ እንደማይበቃ ካሰብክ፤ አንተ ራስህ መሄድ ትችላለህ፡፡ ምክንያቱም እኔ ቀኝ እጄ ብቻ ነው ያለኝ፡፡ ይሉኝታ ይዞህ ይህን የመሰለ ቆንጆ ምሽት የእኔን የተቆረጠ እጅ በማየት ማሳለፍ የለብህም፡፡"

"ኧረ ግዴለም... እኔ እንዲህ አላሰብም፡፡ ሁሉ ነገርሽ ተመችቶኛል፡፡ ጥሎሽ የሄደው ወንድ ያልታደለና የውበት አምላክ ጥሎት የሄደ ለመሆኑ ጥርጥር የለኝም፡፡ የታወረ ነው፡፡ አየሽ..... ዓይኖችሽን ኢላያቸውም፡፡ ጥርሶችሽን አላያቸውም፡፡ አቀማመጥሽ እንኳ፤ ስነ-ልቦናሽ የተሟላ መሆኑን ያሳብቃል፡፡ ምን ታረጊዋለሽ! ያ ያልታደለ ወንድ እድል ከእርሱ ጋር እንዳልሆነች ይወቀው እንግዲህ!" ሰውየው ተንከትክቶ ሳቀ፡፡

ጌራ ከተጨፈናንቀው የዳንስ ወለል መሃል ወጥቶ ወደ ሚሮዳ ሲመለስ ከሰውዬው ጋር መቀመጧን ያውቅ ነበር፡፡

"ይቅርታ!" አለ ጌራ ወደ ሚሮዳ አጎንብሶ፡፡

"በዜማ ብትለው እንኳ አይሰማትም!" አለ ሰውዬው የስላቅ ሳቅ ስቆ፡፡ "ቂ ቂ ቂ ... በዜማ ይቅርታ ብትላት እንኳ እንዲህ በቀላሉ አትቀበልህም፡፡ 'ይቅርታ!' እ?" ሰውዬው የጌራን ድምጽ አስመስሎ አሾፈበት፡፡

"ይቅርታ ጌታው! አልፌ አልፌ አበሳጫለሁ፡፡ እየህ የምታባብለኝ መስሎኝ ነበር፡፡ ግን ይኸውልህ ዝም አለችኝ፡፡ ተመልሼ ከመምጣት በቀር አማራጭ አልነበረኝም፡፡"

"እስኪ ተመልከታት! ሰው የምታባብል ትመስልሃለች? ... አታባብልም፡፡ በዚህች ቆንጆ ሴት ላይ ስንት ዓይኖች እንደዘነቡ መመልከት ያቅትሃል እንዴ? ለማንኛውም አልተሳካልህም፡፡"

ጌራ ወደመጣበት በዝግታ ተመለሰ፡፡ ከመመለሱ በፊት ግን አንድ መልዕክት በዓይኖቹ ለሚሮዳ አስተላልፎ ነበር፡፡ 'መውጣቴ ነው' የሚል፡፡

"መሄዴ ነው፡፡ ትቆያለህ መሰለኝ?" አለችው ወደ ሰውዬው ጎንበስ ብላ፡፡ "ይህ ሰውዬ ... የመዝናናት ስሜቴን ሰርቆታል ባክህ ልሂድ! ከመጣህ ነገም መገናኘት..."

"ካልሽስ እኔም የመቆየት ሀሳብ የለኝም፡፡ መኪና ስለያዝኩ ልሸኝሽም እችላለሁ፡፡ አስተናጋጅ! … ሂሳብ ስንት ነው?" ሰውዬው ሂሳብ ከፍሎ ለመሄድ ተቁነጠነጠ፡፡

ተከትላው ስትወጣ ጌራና "ሴተኛ አዳሪዋ" ተመለከቷት፡፡

"ምን አሰባ ነው?" ጌራ ሴተኛ አዳሪዋን ጠየቃት፡፡ አልመለሰችለትም፡፡ የሆነ ስሜት ግን ፊቷ ላይ ያነበበ መሰለው፡፡

"ከኋላም ቢሆን እንከተላት …" ጌራ በጥድፊያ ሊወጣ ሲል "ሴተኛ አዳሪዋ" እጁን ለቀም አረገችው፡፡ "ስሜታዊ መሆንህን ተገንዝበኸዋል?! በዛ ላይ መውጫ ከፍዬ ልምጣ ስጠኝ፡፡" መውጫ ከፍላ በርሳዋን ይዛ ተመለሰች፡፡

ከጥቂት ደቂቃዎች በኋላ ጌራና ሴቲቷ የምሽት ክለቡን ለቀው ወጡ፡፡ የሰውየው መኪና ግን ሚሮዳን ይዛ ከከባቢው በፍጥነት ተሰውራ ነበር፡፡ ጌራ ቀይዋን ኮሮላ ገብቶ ከለከላት፡፡ ሴቲቷም ተከትላው ገባች፡፡

ፍሎሬንስ፣ ኢጣሊያ

ዝምታን ዝምታ ዋጠው፡፡ ኪራኮስም ዝም ሊሊያ ረጅም ዞማ ፀጉሯን በጣቶቿ ወደ ኋላ አበጥራ አንዳች ነገር ልትናገር አለችና መልሳ ዋጠችው፡፡ ሊሊያም ዝም፡፡ ዓይኖችዋን ወደ ኪራኮስ እየወረወረች በቤቱ ግድግዳ ዙሪያ የተገጠገጡትን መፃህፍት ትቃኛለች፡፡ አልፋ አልፋ ውስጥ የሚተራመሰውን ጥያቄ ከማልመዝመዝ በቀር አፍ አውጥቶ ሊጠይቃት አልከጀለም፡፡ ኪራኮስ ግን አእምሮው መጣች? የሚለው ጥያቄ ቊንቅላቱን ሰብሮ አእምሮውን ሸንቁሮ የመውጣት ያህል ታገለው፡፡ ለምን ቤቴ ድረስ ስተት ብላ

"...በአባትህ ሞት ማዘኔን ልገልፅልህ እወዳለሁ፡፡ ታላቅ ሰው ነበሩ፡፡ አባቴም በጥልቅ ማዘኑ ያስታውቅበታል፡፡ በየቀኑ ሳያነሳቸው አይውልም፡፡ ብዙ እውቀት ያላቸው ሰው እንደነበሩ አጫውቶኛል፡፡" ስትል ሊሊያ ዝምታቸውን ሰበረችው፡፡

"አባትሽና አባቴ ጥሩ ወዳጆች እንደነበሩ አውቃለሁ፡፡ የወንድማማችነት ያህል የጠበቀ ግንኙነት ነበራቸው፡፡"

ሊሊያ ወደ ተቀመጠበት ሶፋ ሄዳ ከጎኑ ተቀምጣ ጫንቃውን ቸብቸብ አደረገችው፡፡ ኪራኮስ ግን ይህ አባባሏ ሊዋጥለት አልቻለም፡፡ የመጣችበት ጉዳይ ይህ እንዳልሆነ ደመነፍሱ ነግሮታል፡፡

"እመሰግናለሁ ሊሊያ፡፡"

"ብዙ ጊዜ እዚህ ብቻህን ማሳለፉ ጥሩ መስሎ አይታሰበኝም፡፡ ሀዘንህ ይገባኛል፡፡ ግን ሲበዛ መልካም አይደለም፡፡እንግዲህ የሚቀጥለውን ቀን ማበላሸት ተገቢ አይመስለኝም፡፡" ብላ ዝም አለችና እንደገና ቀጠለች፡፡ "ኧረ ለመሆኑ ስለ አባትህ ገዳዮች ፖሊሶች ምን ላይ ደረሱ? ..."

"ምንም ላይ አልደረሱም፡፡"

"አንተ በግልህ የደረስክበት ነገር አለ?"

"በፍፁም፡፡"

"አንዳችም ፍንጭ?!"

"አንዳችም፡፡"

"ስለ አባትህ የምታውቀው ምን ያህል ነው?"

"ማለት ..." ኪራኮስ ጥቋቁር አይኖቹን ሰማያዊ ዓይኖቿ ላይ ተከለ፡፡

"ማለቴ አባትህ ምን እንደሚሰሩ ታውቅ ነበር? መቼም ከሥራቸው ጋር የተያያዘ አንዳች ነገር ለእሚሚታቸው ምስጢር ሳይኖር እንደማይቀር እገምታለሁ፡፡"

ኪራኮስ ዓይኖቿ ውስጥ አንዳች ምስጢር ያገኝ ይመስል ዓይኖቹን ሳያላውስ አፍጥጦ ቀረ፡፡ ከአባቱ ሥራ ጋር የተያያዘ ምስጢራዊ እሚሚት? ምን ሊሆን ይችላል? ለመሆኑ የአባቱ ሥራ ምን ነበር?

"ለመሆኑ አባትህ ምን ይሠሩ እንደነበር ታውቃለህ?"

"ምን ማለትሽ ነው?" ኪራኮስ ስለ አባቱ ሥራ ምንም ባለማወቁ ሀፍረት ተሰማው፡፡ "አባቴ በዛ እድሜው ምን ሊሰራ ይችላል? መቼም አደገኛ በሆነውና ከፍተኛ ጉልበት በሚጠይቀው የማዕድን ቁፋሮ ሥራ ውስጥ መሰማራት እንደማይችል አውቃለሁ፡፡ ጉልበቱ ደክሞ፣ ዓይኑ ገጥሞ ነበር፡፡ ያው በጡረታ ደመወዙ ይኖር እንደነበር ነው የማውቀው፡፡" ሊሊያ በኪራኮስ ንግግር ፈገግ አለች፡፡

"እየሀ የጠረጠርኩት ልክ ነበር፡፡ የዋህ ነህ፡፡ አባትህ ለአለፉት አያሌ ዓመታት ፍሎረንስ ውስጥ ሲኖሩ እንዲሁ አልነበረም፡፡ አንድ ምስጢራዊ ድርጅት ከፍተኛ ሥራ ያሠሩቸው ነበር፡፡"

"ምን?!"

"ይህን አታውቅም ብዬ ማሰብ ይከብደኛል፡፡"

"ስለምትይው ነገር ምንም የማውቀው ጉዳይ የለም፡፡ አንቺ እንዴት ልታውቂ ቻልሽ?"

"ሁልጊዜ አሻግሬ ስመለከት ይህን ለመገንዘብ ችያለሁ፡፡ አባትህ አንድ የሚደብቁትና በምስጢር የሚሠሩት ሥራ እንደነበር መገመት ቀላል ነበር፡፡ሰዎች እርሳቸው ዘንድ የሚመጡት በከፍተኛ ጥንቃቄ ነበር፡፡ ይኸን የምልህ አንተን ስሜት ያደረብኝ ከአባቴ ጋር ስለአንተ ጥሩ ወደቤታችን በምትመጣበት ወቅት ነው፡፡ ምንም እንኳ ፀረ-ነጭ አቋም እንዳለህ መሸሸግ ባትችልም፣ ጥሩ ሰብዕናን የተላበስክ ሰው እንደሆንክ አውቅ ነበር፡፡ በዛ ላይ ደግሞ ..." የሊሊያ

ዓይኖች እንዳች ስሜት አፈለቁ፡፡ ከንፈሮቿን ሰብሰብ አድርጋ ስሜቷን ወደ ውስጥ ለመግፋት ሞከረች፡፡ ኪራኮስ የጀመረችውን እንድትጨርስ በመጓጓት ዝም አላት፡፡

"በዛ ላይ ደግሞ ..."ሊሊያ ትንፋሿን ለቃ ቀጠለች፡፡ "ዓይኖቹ ዓይኖችህን ይፈልጉ ነበር፡፡ ምንም ስሜት የምሰጥ ሴት አይደለሁም እንዴ?..... አላውቅም፡፡ ሌላ ወንዶች ፊታቸውን አዙረውብኝ አያውቁም፡፡ ለአንተ ግን ለምን ስሜት እንዳልሰጠሁህ አላውቅም፡፡ ከእኔ ጋር ለመተያየት ብዙ አጋጣሚዎች ተፈጥረውልህ ነበር፡፡ በግልጽ በተገናኘንበት የፓርቲ ዝግጅት ላይ እንኳ አብረን እንደንሳለን የሚል ግምት ነበረኝ፡፡ አንተ ግን ለሚንከራተቱት ዓይኖቼ እውቀህ እይታህን ነፈካቸው፡፡ በዙሪያህ ሳንዣብብ ያዩኝ ሰዎች ሁሉ ፍላጎቴን እስኪረዱት ጥላዬን ጥየብህ ነበር፡፡ አንተ ግን ተሸከረመምክብኝ፡፡ ጉረኛ ነህ ልበል?... ወይስ ከዚህ በፊት የበደለችህ ሴት ነበረች? አባቴ እንኳ ይህን ፍላጎቴን ተረድቶ ብዙ ጊዜ ወደ ቤታችን አንተን ምሣ በመጋበዝ እድሌን እንድሞክር አጋጣሚውን አመቻችቶልኝ ነበር፡፡ አንተ ግን አንትሮፖሎጂ ከሚለው ርዕስ በቀር የምታውቀው ሌላ ዕውቀት ያለህ አትመስልም ነበር፡፡ እስኪ በናትህ አንድ ጥያቄ ልጠይቅህ? ምንም ስሜት አልሰጠሁህም?"

"እንደዛ እንኳ ማለት አልችልም፡፡"

"እና ያ ዘመን ያለፈበት ፀረ-ነጭ አቋምህ ነው ዓይኖችህን የጋረዳቸው? በዛ ላይ እኔ ክልስ እንጂ ነጭ አይደለሁም፡፡"

"ሊሊያ በምትይው ነገር ምክንያት እንኳ አልነበረም፡፡" አለ ኪራኮስ ይህንን ሀሳብ ቋጭቶ ስለ አባቱ ወዳነሳችው ርዕስ ለመመለስ ያህል፡፡ "ደግሞ አትሳሳቺ፡፡ እኔ ነጭን ሁሉ የምጠላ አይደለሁም፡፡ የቀለማቸው ሳይሆን የሴራቸው ጥላቻ ነው ያለብኝ፡፡ አባቴም ቢሆን ቀለማቸውን ሳይሆን ሴራቸውን ሲጠላ የኖረ ሰው ነበር፡፡ ይህ ለእንቺ በቀላሉ ሊገባሽ አይችልም፡፡ ላልተበረዘ አፍሪካዊ ግን ይህ ከግልፅም በላይ ግልፅ ነው፡፡"

"ስማ!" አለች ሊሊያ ይበልጥ ወደ ጎኑ እየተጠጋች፡፡ "አንተ ግን እንደ አባትህ ጥልቅ ሰው አይደለህም፡፡ ያስብከውን ሁሉ ትናገራለህ፡፡ አባትህም ይህን በማወቃቸው የደበቁህ ነገር ሳይኖር አይቀርም፡፡ በዛላይ ደግሞ ሲበዛ ቂል ነህ፡፡ አባትህ በተገደሉበት ቤት ውስጥ ተኝተህ ታንኮራፋለህ፡፡ የአንተን የቀን

ተቀን እንቅስቃሴ የሚከታተሉ ሰዎች መኖራቸውን እንኳ ልትገምት አልቻልክም፡፡ ያሳዝናል፡፡"

"ምንድን ነው የምታወሪው ..."

"በቅርቡ እዚህ አፓርታማ ላይ ተከራይቶ የገባ ሰው ካንተ ላይ ዓይኑን ሳይነቅል እየተከታተለህ ነው፡፡ አሁን የመጣሁት ራስህን እንድታድን እንዳስጠነቅቅህ አእምሮዬ ስላዘዘኝ ብቻ ነው፡፡ እኔና አንተን አሁን በመከታተል ላይ የተጠመዱ ሰዎች እንዳሉ አትጠራጠር፡፡ እኔ እንደሆንኩ ከእንግዲህ ዋጋ የለኝም፡፡ አንዴ በእነዚህ ዓይኖች እይታ ውስጥ ገብቻለሁ፡፡ ግን ..." አለች ሊሊያ በድንጋጤ የሚርገበገቡትን የኪራኮስን ዓይኖች እየተመለከተች፡፡ "ደሞ እንደዚህ የለባበስከው የት ልትሄድ ነው? እብድ ነህ ልበል?" ሊሊያ ልትሄድ ተነሳች፡፡

"ሊሊያ!"

"ከዚህ በላይ ልነግርህ የምችለው ነገር የለም!" በሩን ወርውራ ዘግታበት ወጣች፡፡

# ፱

የተራራው ውስጥ ትርምስ ቀስ በቀስ ቅርፁ እየያዘ መጥቷል፡፡ ከስሜታዊ ንትርክ ወደ ምክንያታዊ ክርክር ገብቷል፡፡ ሆኖም አሁንም ቢሆን አንዳንድ እንጉራዘለል አለመግባባቶች አልጠፉም፡፡

ሚራዥ በበኩሉ እነዚህን አለመግባባቶች እምነታዊ ናቸው በማለት ለማርገብ ጥረት ሲያደርግ ውሎ አድሯል፡፡ ግልጽ አቋም ያልተያዘበት ጉዳይ ቢኖር እንፋለም ወይስ እንደራደር የሚለው ነው፡፡ በሌላ በኩል እንፋለም ነገር ግን ከመፋለማችን በፊት በውስጣችን ያሉትን ቅጥረኞችና ከሀዲዎች እናጥራ የሚል ሀሳብ ተሰነዘረ፡፡

ሚራዥ የእንፋለም ሀሳብ ዋና አራማጅ ቢሆንም ከሀዲዎችን ማጥራት በሚለው ጉዳይ ላይ ግን ሀሳቡን ከወጣና ከወረደ በኋላ ቀዝቃዛ አቋም አሳይቷል፡፡ ይህን አቋም ከያዙት በኩል ለምን ሀሳቡን እንደቀየረ እንዲያስረዳ ሲጠየቅ የተናገረው ፈገግ የሚያስብል ነበር፡፡ ምናልባትም ሰሞኑን በተራራው ውስጥ ጨፍገግ እንጂ ፈገግ ያለ ፊት ታይቶ ስለማይታወቅ ይህ የመጀመሪያው ፈገግታ ሳይሆን አይቀርም፡፡ ለምን ሀሳብህን ቀየርክ ተብሎ ሲጠየቅ፡ "ሀሳቡን የማይቀይር አስክሬን ብቻ ነው፡፡" በማለት ነበር በደፈናው የተናገረው፡፡ ነገር ግን በዚህ አባባሉ ብቻ የለቀቀው የለም፡፡ ምክንያቱን በግልፅ እንዲያስቀምጥ የሚያፋጥጡ ድምጾች በረከቱ፡፡

በተለይ ሳዶፍ በሚል የምስጢር ስም ሚታወቀውና ሲ.አይ.ኤ ውስጥ በምርጥ አልሞ ተኳሽነቱ ይታወቅ የነበረው አባል ሚራዥን በቀላሉ ሊለቀው አልቻለም፡፡

"እየውልህ ሚራዥ እኔ በጆርቶጋዳ ተመልምዬ ወደ ኢትዮጵያ ከመጣሁ ድፍን አስራ ሁለት ዓመታት አልፈዋል፡፡ እስካሁን የፈየድኩት አንዳች ነገር የለም፡፡ ይኸው እዚህ ተራራ ውስጥ ተቀምጬ እቀለባለሁ፡፡ አንዳንዴ ለምን ሞቅ ወዳለና ፋይዳ ወዳለው ትግል አንገባም? የሚል ጥያቄ ዘወትር

አሁን ሰዓቱ የደረሰ ይመስለኛል፡፡ ሆኖም ይፈጠርብኛል፡፡ ብቻም ሳይሆን፣ ጦርነት ናፋቂም ጦርነት ናፋቂ ላለመባል አቋሜን አላሳወቅሁም፡፡ ነገር ግን ለምን ስላልሆንኩ ይህንን እልሳተፍም? የሚል ጥያቄ ፋይዳ ያለው አጥሬሽን ውስጥ ጊዜውን ጠብቆ ደረሰ፡፡ ይፈጠርብኛል፡፡ ሰዓቱ ደግሞ ይኸው ባላውቅም ታላቅ ጀብዱ እንደምታሰልፉኝ በየትኛው ግንባር ነገር ግን በውስጣችን ያሉ ከሀድያን ለመፈፀም ተዘጋጅቻለሁ፡፡ ደረስ ፍልሚያውን መጀመር ዋጋ የለውም፡፡" እስካልተመነጠሩ ሲል እንቅጩን ተናገረ፡፡

"ጠላቶቻችን ሊውጡን ባሰፈሰፉበት በዚህ ሰዓት እርስ በእርስ መናቆራችን ለጠላቶቻችን እድል መስጠት ነው፡፡ በየትኛው መረጃ ነው ከሀዲውን መንጥረን ማውጣት የምንችለው? በዚህ አጭር ጊዜ ውስጥ ረጅም ጊዜ የሚፈጀውን ምርመራ አድርገን ከሀዲውን ከእውነተኛው መለየት ይቻላል? ወይስ በግምት መልክ እያየን ይህ ከሀዲ ይመስለኛል ይኸኛው አይደለም ልንባባል ነው?" ሚራዥ መልሶ ጠየቀው፡፡

"በዚህ ሁኔታ ብንዋጋ፣ የውጊያ ስልታችንም ሆነ ወታደራዊ ብቃታችን በከሀዲዎች በኩል ሊሄድ ስለሚችል ጦርነቱን አናሸንፍም፡፡" ሳዶፍ እንደገና አፋጠጠው፡፡

"እነማንን በየትኛው ሚዛን ከሀዲ ልንል ነው ታዲያ?"

"ለምሳሌ አማዲዎ ከዶናል፡፡ ከአማዲዎ ጀርባ እነማን እንደነበሩ ማጣራት ተገቢ ይመስለኛል፡፡"

"አማዲዎ በግሉ ካደን እንጂ በቡድን አይደለም፡፡ አብሮት የኮበለለው ሰውም ቢሆን ይህን ያህል ድርጅቱን አደጋ ላይ ሊጥል የሚችል ሰው አልነበረም፡፡"

"አሁንም አዳዲስ መረጃዎች እየወጡ ነው! እዚህ ሆኖ መረጃ የሚያቀብል አለ ማለት ነው!" ሳዶፍ ወደ ሚራዥ አንገቱን እንደ አንቴና መዞ በብሽቀት ተነፈሰ፡፡ "ሚራዥ! …ይቅርታ አድርግልኝ እኔ ስሜታዊ ሰው አይደለሁም፡፡ … ሆኖም በመረጋጋት ውስጥ ያለውን መቀደም ጠንቅቁ የማውቅ ሰው ነኝ፡፡ የድርጅቱ ዓላማ ምን እንደሆነ ሁሉ የዘነጋችሁት ይመስለኛል፡፡ ዴርቶጋዳ ሲያቅማማ ታይቶም ተሰምቶም አይታወቅም! ጠላቶቻችን እጆቻችንን ሊይዙ ከበውናል፡፡ ከዚህ የበለጠ ጥቃት የለም፡፡ ለምን? እነማን? እንዴት? የሚለውን መልስ በመፈለግ ጊዜ ማባከን ያለብን አይመስለኝም፡፡ ከሀዲዎች ባፋጣኝ መያዝ አለባቸው፡፡ እነ ይሁዳ ጉንጫችንን

እየሳሙ እስኪሸጡን ድረስ መጠበቅ ያለብን አይመስለኝም፡፡ ኢትዮጵያን ለኢትዮጵያውን መመለስ የሚቻለው በዚህ ትህትና አይደለም፡፡ በጦርነት ውስጥ ትህትናውን ለማሳየት የሚጥር ድርጅት በውሃ ላይ እየተንሳፈፈ በራሱ አትጣጫ ለመንዝ እንደሚከጅል ኩበት ነው፡፡ ከዚህ የበለጠ ጅልነት የለም፡፡ የብዙዎቻችን የልጅነት ታሪካችን ሳይቀር ተጋልጧል፣ የበላናት፣ የጠጣናት አልቀረችም፣ የወጣናት፣ የወረድናት አልተሸሸገችም! ይህን ሁሉ አንድ ሰው የተናገረው ይመስልሃል? በዚህ ክህደት ውስጥ አማዲዎ ብቻ ሳይሆን የድርጅቱ ቁልፍ ሰውም እንዳለበት አትጠራጠር፡፡ ድርጅቱ በውስጡ ያሉትንና መረጃ የሚያቀብሉትን መመንጠር የመጀመሪያ ሥራው ማድረግ ይኖርበታል፡፡ አለበለዚያ እኔ ሳዶፍ እዚህ ስንደፋደፍ አልያዝም፡፡ ከብዙ እሳት የተተፋሁ የእሳት እራት ነኝ፡፡ እመነኝ ሚራዥ! እኔ እዚህ ለድፍን አሥራ ሁለት ዓመታት ትዳሬን፣ ልጆቼን፣ ጓደኞቼን ጥዬ የተቀመጥኩት ለሀገሬ እንዳች ተስፋ ለመፈንጠቅና ለዚሁ ተስፋ ሕይወቴን እንደጧፍ አንድጄ ለወደድኩት ዓላማ ብርሃን ለመሆን ነው፡፡ ግን አልሆነም፡፡ አልሆነም፡፡ "የኢትዮጵያ ትንሣኤ የቀረበ መስሎኝ ነበር፡፡ ተሞኝቻለሁ፡፡ ይቺ የተረገመች ሀገር የእርሷ ዘመን መቼ እንደሚመጣ አላውቅም፡፡ ሚራዥ! … አንተ በዚህ የተራራ ከርስምድር ውስጥ ተስሚነት ካላቸው ጥቂት ሰዎች አንዱ ነህ፡፡ እያንዳንዱ የተራራው ነዋሪ በአንተ ውስጥ አባትህን ይመለከታል፡፡ እንደ አባትህ እንደ አባ ጀንበሩ ያምንሃል፡፡ ይሰማሃል፡፡ ከሻጊዝ በላይ ተሰሚነት አለህ፡፡ በዚህ ተራራ ውስጥ ያሉትን ህልሞች የማዳን ሥልጣን በእጅህ ላይ ነው፡፡ አዝናለሁ፣ አንተ ግን ትህትናህ በዝቷል፡፡" ሳዶፍ ሚራዥን በቆመበት ጥሎት ሄደ፡፡ ሚራዥ ለእያሌ ደቂቃዎች አቀርቅሮ በቆመበት ከቆየ በኋላ ወደ ሻጊዝ ቢሮ ገሰገሰ፡፡

## አዲስ አበባ፣ ኢትዮጵያ

"ሜሮዳ! ዝነኛዋ ሰላይ! ...ቂቂቂ... ያንቺን አንገት ለመፈጥረት በመንከራተት ብዙ ቀናትን ከእድሜዬ ላይ ቀንሻለሁ! የጊዜ መልካም ፈቃድ ሆኖ እነሆ ዛሬ ተገናኘን፡፡ እንተዋወቅ!" አላት መኪናውን በፍጥነት እያሽከረከረ፡፡ ጋቢናው ውስጥ ከመግባቷ ነበር ሁለት ጠብደል ጠብደል ሰዎች ከኋላዋ ሽጉጦቻቸውን አቀባብለው ከጀርባዋ የደቀኑባት፡፡ አንደኛው ከጀርባዋ በልቧ ትክክል፤ ሊላኛው ከቀኝ እጇ ብቃይ ላይ፡፡ አስቀድመው በደንብ እንደተዘጋጁበት ገባት፡፡

"ሜሮዳ! ዝነኛዋ! ለሀገሬ ቀኝ እጇ በቂ ነው ያልሽዋ ውብ! ግን አደገኛዋና ሞገደኛዋ ሴት! እንተዋወቅ! እኔን በቅጽል ስሜ ታውቂኛለሽ፡፡ ቀንጠፋው! በእርግጥም ስታጠምጂኝ ነበር፡፡ የምገኝበትንም በትክክል አውቀሽዋል፡፡ ስሜም ከቅጽልነት ወደ ስምነት መለወጡን ደርሰሽበታል፤ እየውልሽ ቀንጠፋው እኔ ነኝ፡፡ ነገር ግን ቀን የጠፋበትን ብቻ ሳይሆን መንገድ የጠፋበትን ሁሉ እይዛለሁ፡፡ ለቀም! 'የማንም ልቅምቅም የሰው ልክ አያውቅም!' ይላል ቀንጣፋው ቀን ለጠፋው! እየሽ እኔን ተራ ቢራ ገልባጭ አርገሽ ቆጥረሽኝ ነበር፡፡ ዝነኛዋ ሜሮዳን በመያዜ እድለኛ ነኝ፡፡" አለ ቀንጣፋው የመኪናውን መሪ እያጠማዘዘ፡፡

"እንኳን ደስ ያለህ!" አለችው ሜሮዳ የመንገዱን ግራና ቀኝ እየተመለከተች፡፡ ካፊያ ነው፡፡ አመዳሙ አስፋልት በዝናቡ ነጠብጣብ ፊቱን ማባበስ ጀምሯል፡፡

"ግራ ቀኙን ተመልከቺ ያንቺ ምሽት አይደለም፡፡ ምሽቱ ዝናባማ ነው፡፡ እንቺም እኔ ላይ ዘንበሻል፡፡ በተራራው ዙሪያም እንዲሁ እያካፋ ነው፡፡ ሃ ሃ ሃ ..."

ቦሌን ለቀው ሸቅብ ወደ ሃያ ሁለት ይወነጩፉ ጀመር፡፡ ሜሮዳ በድን የሆነች መሰላት፡፡

# ፲፩

አማዲዎ የቀረበለትን ቢጫ ገጽ በዴርቶጋዳ አባላት ስም ዝርዝር ሞላው፡፡ ከጀርባው ቆመው ይህን ጉድ እያዩ የሚብረከረኩት ጠባቂዎቹ ማወቅ የቻሉት እስከአሁን ስማቸው ከዚህ ቢጫ ገጽ ላይ አለመስፈሩን ብቻ ነው፡፡ በሚቀጥሉት ደቂቃዎች ግን ስማቸው ሁሉ ላለመመዝገቡ ማረጋገጫ የላቸውም፡፡ እስካሁን እንኳ አማዲዎ ለምን ይህን ስህተት እንዳልተሳሳተ ሊገባቸው አልቻለም፡፡

ቀንጠፋውም፡ ተጨማሪ ወረቀቶችን ይዞ እስከአሁን ለምን እንዳልተመለሰ ሊገባቸው አልቻለም፡፡ ምናልባት እንደልማዱ አንዱን ግድግዳ ተደግፎ እያጨሰ ወይም ሊጠጣ ሄዶ ይሆናል ሲሉ ተስፋ አድርገዋል፡፡ አልያም የሚፈልገውን መረጃ አግኝቶ እንደሄደ ገምተዋል፡፡ ወይም ቢጫውን ገጽ እስካሁን ይጨርሰዋል የሚል ግምት ስለሌለውም ይሆናል ሲሉ አስበዋል፡፡ ያም ሆነ ይህ ቀንጠፋው ቢጫዎቹን ወረቀቶች በሚቀጥሉት ደቂቃዎች ውስጥ ይዟቸው እንደሚመጣ አልተጠራጠሩም፡፡

አንደኛው ደህንነት መርበትበቱ በግልጽ ታወቀበት፡፡ ሽጉጡን የያዙት እጆቹ ወባ እንደያዘው ቆለኛ እስክስታ ይመቱ ጀመር፡፡ ስሙ በዚህ መዝገብ ላይ ከሰፈረ በቀላሉ እንኳ የሚገለው አያገኝም፡፡ ከጥጉ ወደቆመው ጓደኛው ተመለከተ፡፡ እሱም ጣር እንደያዘው ሟች ግንባሩን ላብ ወርጭቶበታል፡፡

"ልመታው ነው፡፡" ሲል በምልክት ነገረው፡፡

ራሱን በአዎንታ ነቀነቀለት፡፡

አማዲዎ የቢጫውን ገፅ ጀርባም በስም ሊሞላው ምንም አልቀረው፡፡ እነዚህኞቹን በፊት ለፊት ባይመዘግባቸው እንኳ በጀርባው እነሱን ጨምሮ በደህንነት መስሪያ ቤቱ ሰርገው የገቡትን ሁሉ እንደሚመዘግብ አልተጠራጠሩም፡፡ ሌላው ይቅርና ከዳግማዊ ጀምሮ በደህንነት መስሪያ ቤቱ ከተሠገሡጉት

የደህንነት መስሪያ ቤቱ ሰዎች አንዱ ከተጋለጠ ሌላው በምርመራ እንደ ማይደረስበት ምንም ማረጋገጫ የለም፡፡

"አንተ 'ማትረባ ከሀዲ፣ አምልጥ!" አለው አንደኛው ሊተኩስ እጁ እየተንቀጠቀጠ፡፡

"አማዲዎ አምልጥ! ተነሳና ሩጥ!" አለው ሁለተኛው፡፡ "ወደ በሩ ሩጥ! አንተ ክፉ ከሀዲ አምልጥ! የዚህ ሁሉ ክህደትህ ምክንያት እንኳን ለኛ ለአንተ እንኳ ግልጽ አይደለም፡፡" አማዲዎ ፊቱን ሳያዞር ተነስቶ ቆመ፡፡ "በማንኛውም ሰው ልብ ውስጥ ያለውን ቋጠሮ ማንም አያውቅም!" ሲል በቆመበት ተናገረ፡፡

"አንተ የተረገምክ ርጉም እንዳተ ያለ ከሀዲ ምንም ዓይነት ልብ የለውም! አማዲዎ አምልጥ!... ሩጥ!"

አማዲዎ ወደበሩ ተራመደ፡፡ የበሩን ጉበን ጨብጦ በሩን ሊከፍት ሲል አንዳች የሚያቃጥል ነገር ተሰማው፡፡ አንደኛው ደህንነት አከታትሎ የተኮሳቸው ጥይቶች ጭንቅላቱን ከኋላው ወንፊት አደረጉት፡፡ አማዲዎ መውደቁን ሲያረጋግጥ ራሱ ላይ ሽጉጡን ደቀነው፡፡ ሁለተኛው ደህንነት ሊያስቆመው አፉን ከመክፈቱ ምላጩን ሳበው፡፡ መሬት ላይ ከመዘረሩ ሁለተኛው ደህንነት ቢሜውን ወረቀት ከጠረጴዛው ላይ ላፍ አርጎ ወደ አማዲዎ ሮጦ አፉ ውስጥ ጠቀጠቀው፡፡ በፍጥነትም የሟቹን ደህንነት ሽጉጥ አንስቶ ለአማዲዎ በድን አስጨበጠው፡፡

በግምት ይህ ከሆነ ከአርባ ያህል ደቂቃዎች በኋላ ከንድና ክንዷን የፊጥኝ የታሰረች ሴት ገርበብ ባለው በር ተንደፋደፋ ገብታ ከወደቁት አስከሬኖች መሀል ወደቀች፡፡ በትዕበት ቀንጠፋው ከሌላ ሁለት ደህንነቶች ጋር ተከታትሎ ገባ፡፡ ውስጥ የቆየው ደህንነት፣ ባይኑ የሚያየውን ማመን አልቻለም፡፡ ይህቺ ሴት ሜሮዳ መሆኗንም ሆነ መያዟን ለማመን አቃተው፡፡

ቀንጣፋው የሆነውን ሁሉ ከተመለከተ በኋላ በዝግታ ቀና ብሎ ጠባቂውን ተመለከተው፡፡

"...ሊ...ሊ...ሊያመልጥ ሲል ነው፡፡" ጠባቂው በመርበትበት መለሰ፡፡

"እየውልህ ነግሬአችሁ ነበር፡፡..... እናንተ ነፈዞች...... ጉድ ሊሠሩን እንደሚችል እገምት ነበር፡፡ እሺ. እሺ. የሚልን ሰው ድሮም እፈራለሁ!" ቀንጠፋው የወደቀውን ግዳይ ቁልቁል እየተመለከተ ራሱን ወዘወዘ፡፡

"ታገለን! ታገለን! በመጨረሻም የዚህ ሰው ሽጉጥ እጁ ውስጥ ገባ፡፡ የራሱን ሽጉጥ ቀምቶ ከመታው በኋላ ቢላውን ወረቀት ጎርሶ እያላመጠ ወደ በሩ ሲሮጥ በተከታታይ ተኮስኩበት፤ ወደቀ" የተረፈው ደህንነት የፈጠራውን ታሪክ በተቻለው መጠን ለማጣፈጥ ሞከረ፡፡

"ለመሆኑ ወረቀቱን በጣም አላምጦት ይሆንን" ቀንጠፋው ከአማዲዎ አፍ ውስጥ የተጎደጎደውን ወረቀት በመሃረቡ ቆንጥጦ እያወጣ ጠየቀ፡፡

"እያይ! ... ገና ሸብልሎ ከመጉረሱ ነው የመታሁት፡፡ በደንብ ያላመጠው አልመሰለኝም፡፡"

"እዎ ..." አለ ቀንጠፋው ከአማዲዎ አፍ ውስጥ የመዘዘውንና የተወቀጠ ያህል የተጨመታተረውን ወረቀት እየፈታታ፡፡"ቀድመኸዋል! በደንብ አላላመጠውም እየኸው ... አዎ ... ጥሩ መዝግቧል ባክህ? በአንደኛው ገጽ ብቻ.......፡፡ በሁለተኛው ገጽ..... ጥሩ ነው፡፡ ታታሪ ሠራተኛ እንደነበር ያስታውቃል፡፡"

ሲጋራውን እየማገ ጨርመትመት ያለውን ወረቀት ሲፈታታ ቆይቶ የስም ዝርዝሮችን እየተመለከተ ፈገግ አለ፡፡

የአማዲዎ መዝገብ ተራ ስም ዝርዝር ብቻ ሳይሆን የቅንፍ ውስጥ ተጨማሪ ማስታወሻም ነበረው፡፡

<u>ኢ/ር ሻጊዝ እጅጉ፡-</u> (ሞቷል ተብሎ የተቀበረው ህያው ሰው፡፡ የደም ዓይነት 'o'፡፡

ሎስ አላሞስ ውስጥ በተደረገለት የፊት ቀዶ ጥገና የዣክ ዶናልድ ሲሞንን ፊት አጥልቆ የሚኖር፣ በተገነጠለው ገጽ ኦፕሬሽን ወደ ተራራው መጥቶ አሁን እዛው ይኖራል)

<u>ዶ/ር ሚራዥ ዠንበሩ፡-</u> (አባቱ የዱሮቶጋዳ መሥራችና በድርጅቱ ዘንድም እንደ ጣኦት የሚመለኩ ናቸው፡፡ ሚራዥ

የደም ዓይነቱ 'A' የቀድሞው ሠራዊት አባል፣ አሁን እንጌ የተሰኘ ሰርጅን)

<u>ቢጻራ ፊንሐስ</u> ፡- (ቢጻራ ያደገችው ማና ሐይት ውስጥ በሚገኘውና እንጦንስ በሚባለው የሴቶች ገዳም ውስጥ ነው፡፡ አባቷ ቤተ እስራኤላዊ ሲሆን ወደ እስራኤል ሲጓዙ በረሀ ውስጥ ጊንጥና እባብ ነድፏቸው አርፈዋል፡፡ እርሷ ግን ወደ እስራኤል ተጉዛ እዛው እስራኤል ሀገር ውስጥ ትምህርቷን ከማጠናቀቋም በላይ ግዴታ የሆነውን ወታደራዊ ሥልጠና የወሰደች ናት፡፡ በኋላም የሞሳድ አባል ሆና አገልግላለች፡፡ ከሚራዥ አርግዛለች፤ልትወልድም ተቃርባለች)

<u>ጌራ፡-</u> (የአባቱን ስም አላውቅም፡፡ የአሜሪካ አየር ኃይል አባል ነበር፡፡ ድርጅቱ ከመለመለው በኋላ ወደ ኢትዮጵያ መጥቶ ዴር33 የምትባለዋንና በምድር፣ በአየርና በባህር የምትጓዘውን ረቂቅ አውሮፕላን አብራሪ ነው)

<u>ሜሮዳ</u>፡- (የሷንም፣ የአባቷንም ስም አላውቀውም! ሜሮዳ የአዲስ አበባ ተወላጅ ናት፡፡ እናቷ ሴተኛ አዳሪ ነበረች፡፡ ሲ.አይ.ኤ. ኢትዮጵያ ውስጥ ከመለመላት በኋላ አሜሪካ ውስጥ ብቻም ሳይሆን በተለያዩ የዓለም ሀገራት ስትሰልል የኖረች ቀልጣፋ ሴት ናት፡፡ ውበቷ ልዩ በመሆኑ ማንንም ታማልላለች፡፡ በዘመቻ የተገነጠለው ግራ እጇ፣ ቢቆረጥም ውበቷን አልቀነሰውም)

<u>ፕሮፌሰር በርናባስ፡-</u>(እኚህ ምሁር በዴርቶጋዳ ውስጥ ያለውንና ሁለተኛውን ህዋስ ማለትም ራማቶሓራ የተሰኘውን ክፍል የሚመሩ ተመራማሪ ናቸው፡፡ የልዕለ አእምሮውን ክኒን በማምረቱ ረገድ ከፍተኛውን ድርሻ የያዙ ተመራማሪ ከመሆናቸውም በላይ፣ አሁን በተራራው ውስጥ እድሜያቸው ከገፉ ሽማግሌዎች አንዱ ይሁኑ እንጂ፣ ተሰሚነታቸው ላቅ ካሉት መካከል አንዱ እንደሆኑ ይታወቃል)

<u>ዶ/ር ዣንጊዳ፡-</u> (የአባቱን ስም አላውቅም፡፡ ይህም ካለማወቁ የተነሳ እንጂ መደበቁ አይደለም፡፡ ይህ ዶክተር የቀድሞው ጦር አባል ነው፡፡ ከሚራዥ ጋር ጠፉን ከድቶ በሜሮዳ ረዳትነት አሜሪካ የገባ ሰው ነው፡፡ በተራራው ውስጥ ሤምት ከሚባሉት ሰዎች አንዱ ይሁን እንጂ ተሰሚነቱ አጠያያቂ አይደለም፡፡ ከሚራዥ ጋርም ከወንድምነት ያለፈ ፍቅር አላቸው)

<u>ኪራኮስ ባኮስ፡-</u> (ይህ ሰው የአውሮጳውን የዴርቶጋዳ ህዋስ ማለትም ዣንቶዣራ እየተባለ የሚጠራውን ክፍል እንዲመራ

አደራ የተጣለበት ምሁር ነው፡፡ ጥንታዊውን የኢትዮጵያ ስልጣኔ የሚመራመር ዣንቶግሮ የተባለው ሀምራዊ አብዛኛውን ጊዜ ከድርጅቱ የዕለት ተዕለት ሥራ ላይ ባይሳተፍም፣ የተደበቀውን የዕለት ተዕለት ሥራ ነው፡፡ ከኢትዮጵያ ውጪ በስርቆት ስልጣኔ በየዋሻውና ሥራ ላይ ያፈላልጋል፡፡ አባቱ ትግራይ ውስጥ የተወሰዱ ጥንታዊ በተለይም ኑሮአቸውን ጣሊያን ፍሎረንስ ውስጥ ነው ትውልዳቸው-እጋሚ፡፡ አስቆጥረዋል..) እነዚህን ብቻ ሳይሆን ነረት እያሌ ዓመታትን ከቅንፍ ማስታወሻና ከሥራ ድርሻ ጋር አያሌ የዴርቶጋዳ አባላትን ዋቆ ማርዬ፣ እነ አንጎታ፣ እነ አድያም ... እነ ሳዶፍ...

ከፍርሀቱ የተነሳም ይሁን ወይም የድርጅቱን አባላት ሁሉ ለማስጨረስ ካለው የግል ፍላጎት ወይንም፣ በልቡ ውስጥ ማንም እንዳይደርስበት ተደርጎ በተቀበረ እንዳች ምክንያት ባይታወቅም ቀንጠፋው አእምሮው ውስጥ ያለውን ሁሉ ያነበበት ይመስል ወረቀቱን ለማብቃቃት ፊደሎቹን እንደጨፍ አሳንሶ ነበር የወረቀቱን ፊትና ጀርባ ጠቅጥቆ የሞላው፡፡

ቀንጠፋው፣ ቢጫውን መዝገብ ሲያይ ከቆየ በኋላ እንደገና ሲጋራውን ምሳ ወደ ተሰብሳቢዎቹ ተመለከተ፡፡ ጭሱን በዝግታ ከለቀቀ በኋላ ሁሉንም በየተራ ቃኝቶ ይናገር ጀመር፡፡

"ይህ ቢጫ መዝገብ ..." ሲል ጀመረ የተጨማተረውን ወረቀት በግራ እጁ ከፍ አርጎ ለሁሉም እያሳየ፡፡ "ይህ ቢጫ መዝገብ ብዙ የዴርቶጋዳ አባላትን ስም ዝርዝር የያዘ ነው... በሺህ አባዙት፡፡ ምክንያቱም አንዱን ስንይዝ ሺሁን ያጋልጣል፡፡" በለበጣ ፈገግ አለ፡፡ ከፍተኛ ድል እንደተቀዳጁ ለማሳየት ያህል ወደኋላ ለጠጥ ብሎ በመቀመጥ ሁሉንም በየተራ ቃኘ፡፡

"ዓላማችን..." አለ ሌላ ሲጋራ ለማውጣት የቀኝ ኪሱን እየበረበረ፡፡ አንዲት ወገቧ የተለጋ ሲጋራ አውጥቶ በከንፈሮቹ ካጣበቀ በኋላ አሁንም "ዓላማችን...." ሲል ወትሮም የወገብ ስብራት ያጋጠማት ሲጋራ ይባሱን ልትሰበር ስትል በአገጩ ደግፎ አስቀራት፡፡ ላይተፉን ፈልጎ እንዳወጣ ወገበ ሰባራዋን ሲጋራ ስብራቷን ቆምጦ ጥሎ ቀሪዋን ለኩሳት፡፡ "ዓላማችን፣ በዚህ ቢጫ መዝገብ ላይ የሠፈሩትን ስሞች መሠረዝ ብቻ አይደለም፣ የዕዝ ማዕከላቸው የሆነውን ተራራም ወደ አመድነት

መለወጥ ነው፡፡ ነገር ግን ሁሉም የዕዝ ማዕከሎቻቸው እስኪታወቁ ድረስ መቸኮል የለብንም፡፡ ሁሉም አባላቶቻቸው እስኪታወቁ ድረስም ከኋላቸው እንደ ጥላቸው ያለ አንዳች ኮሽታ ልንከተላቸው ይገባል፡፡ እደግመዋለሁ! ከኋላቸው እንደጥላቸው ያለ አንዳች ኮሽታ... ልንከተላቸው ይገባል፡፡ እንደፍልፈል በየተራራው አፈር እየገፉ ከጉድጓድ ጉድጓድ እየዘለሉ ምን ያህል ይኖራሉ?! ...ጨርሻለሁ፡፡" ብሎ ቀንጠፋው በድቁሻ ብዛት ወደላመችው ሚሮዳ ቁልቁል ተመለከተ፡፡ ነፍሷን የሳተች ያህል ተዘረጋግታለች፡፡ "ስሙ! ይህችን ሴት ያሥር ሰዎችን ያህል መጠበቃችሁን እንዳትዘነጉ፡፡......" ወረቀቱን ይዞ ውልቅ አለ፡፡

# ፲፪

## ፍሎረንስ

ኪራኮስ፣ በሁለት ነገሮች መሀል ተጣብቆ ነበር ቀኑን ያሳለፈው፡፡ በአንድ በኩል የሚሄርዳ ትእዛዝ ከቤቱ እንዳይወጣና ከማንም ጋር እንዳይገናኝ አግዶታል፡፡ በሌላ በኩል ሊሊያ የነገረችው ምስጢር አካባቢውን በፍጥነት ለቆ እንዲሰወር እየገፋፋው ነበር፡፡ ሆኖም ከአካባቢው የመሰወሩ ሀሳብ እያየለበት መጥቷል፡፡ ይህን ሲያወጣ ሲያወርድ ከቆየ በኋላ ቤቱን ለቆ ከመውጣቱ በፊት ይዞት ስለሚሄደው ነገር ማሰብ ጀመረ፡፡

በግድግዳው ዙሪያ የተገጠገጡትን መጻህፍት እየዞረ ሲያስስ ቆይቶ የቱን ይዞ የቱን ትቶ እንደሚሄድ ግራ ገባው፡፡ የዳንቴ አሊጊዬሪን "ገሀነመ እሳት" የተሰኘውን ጥንታዊ መጽሀፍ እንደዘበት አንስቶ አመሀሉ ላይ ገለጠው፡፡ "አንቺ ውቢት ፍሎረንስ ሆይ፤ ጋኖች አልቀው ምንቾቶች ጋን የሆኑብሽ፣ አዲሶች የዘመኑ ሰዎች ባጭር ጊዜ ውስጥ ገንዘብ በማከማቸት ጌታ ሆነው ትዕቢት ያደረባቸው ጥጋበኞችና ግፈኞች በውስጥሽ ስለረቡ በጣም ታፀፅቺለሽ፡፡" ከሚለው ሀረፍተ ነገር ጋር ተገናኘ፡፡

ወደ መስኮቱ ተራምዶ መጋረጃውን ከገለጠ በኋላ፣ የእርሳን ወንዝ ቁልቁል እየተመለከተ "ፍሎረንስ" የሚለውን ቃል "ኢትዮጵያ" በሚለው ተክቶ እንደገና አነበበው፡፡

"አንቺ ውቢት ኢትዮጵያ ሆይ፤ ጋኖች አልቀው ምንቾቶች
ጋን የሆኑብሽ፤ አዲሶች የዘመኑ ሰዎች ባጭር ጊዜ ውስጥ ገንዘብ
በማከማቸት ጌታ ሆነው ትዕቢት ያደረባቸው ጥጋበኞችና
ግፈኞች በውስጥሽ ስለረቡ በጣም ታፀፅቺለሽ፡፡"

እየመሸ በመሆኑ የአርኖ ወንዝ፣ በምሽቷ ጀምበር ጨረሮች የወርቅ ገዝር መስሏል፡፡ ሊሊያም የክፍሏን መስኮት ከፍታ ወንዙን እየተመለከተች ነበር፡፡ ኪራኮስ የአርኖን ወንዝ ብቻ ሳይሆን እግረ መንገዱን ሊሊያንም እየተሰናበተ ነው፡፡ ኢትዮጵያ ውስጥም በስም ተመሳሳይ የሆነ ወንዝ እንዳለ እስታውሱ አርኖ የሚባል፡፡ ከባህርዳር ወደ ጎንደር በተነጠፈው አውራ ጎዳና ላይ አዲስ ዘመን የተባለችውን አነስተኛ ከተማና ጣራ ገዳም የተሰኘውን ተራራ አልፎ የሚገኝ ወንዝ ነው፡፡ ከጣራ ገዳም ወረድ ብሎ ያለውን የገጠር ቀበሌ አቋርጦ የሚያልፈው ወንዝ፡፡ ይኸኛውን አርኖ ሲያይ ሁልጊዜም የጣው አርኖም ከአዲስ ዘመን ተራሮች ጋር ድቅን ይሉበታል፡፡ ለምን ስማቸው እንደተመሳሰለ እስካሁን ማንም ባያስረዳውም ጣልያኖች ኢትዮጵያን ሲወሩ ሊሰይሙት እንደሚችሉ ገምቷል፡፡ ከኢትዮጵያው አርኖ ወደ ፍሎረንሱ አርኖ ዓይኖቹን መለሰ፡፡

የአርኖ ወንዝ የፍሎረንስ ሳሀይ ነው - የጥንታዊቷ ከተማ መሠረትና ውበት፡፡ አርኖ ከፋልቴሮና ተራራ እምብርት ይመነጭና ወደ ደቡብ ከተጓዘ በኋላ ወደ ምዕራብ ታጥፎ እንደ ዘንዶ እየተጥመለመለ ፍሎረንስን ይሰነጥቅና የመቶ ሃምሳ ማይል ሩጫውን ፈፅሞ ሊጉሪያን ባህር ውስጥ ይሰጥማል፡፡ አርኖ ፍሎረንስን ሲያቋርጥ ታዲያ እጅግ ድንቅና ስመጥር ድልድዮችን እንደመቀነት ሸብ አርጎ ነው፡፡ በሚካኤል አንጀሎ ውትወታ የተሠራው ሳንታ ትሪንታ የተባለውና አሁን ወደታች ኪራኮስ አቆልቁሎ የሚያየው ፖንቴ ቬኪዮ የተባሉት ድልድዮች የአርኖ ዝናሮች የፍሎረንስ ጌጦች ናቸው፡፡

በእንግሊዝ የቴምስ ወንዝ፣ በአሜሪካ የሚሲሲፒ ወንዝ የበርካታ የጥበብ ሰዎችን ዓይን እንደከፈቱ ሁሉ በኢጣሊያም የአርኖ ወንዝ የበርካታ ጠበብቶች አባት ነው፡፡ የነ ዳንቴ አሊጌዬሪ፣ የነሚካኤል አንጀሎ… የጥበብ ዓይኖች የተገለጡት በአርኖ ወንዝ ወርቃማ ጨረሮች ነው፡፡ ፍሎረንስን የበርካታ ሰዓሊያን፣ ገጣምያንና ደራሲያን መፈልፈያ ያረጋትን አርኖን ቁልቁል ሲመለከት የቆየው ኪራኮስ እንድ ሃሳብ በወርቃማው ውሃ ላይ ሲንሳፈፍ በዓይነ ህሊናው ውልብ አለለት፡፡ "Renaissance" ወይም ዳግም ልደት በመባል የሚታወቀው የመነሳሳት ዘመንም እንደ

አውሮጳን ከጨለማው ዘመን የመነጠቃትን ዘመን እንስቶ ሀዳሴ፡፡

የዳግም ልደት የትውልድ ቦታ፣ የኪነ-ጥንታዊቷ ፍሎረንስ እናት ትሁን እንጂ ጥንታዊውን ስልጤ ጥበብና የኪነ-ህንፃ ስልጣኔዋም በማሸብረቅ ላይ እንደሆነ ያላገለለ ዘመናዊ ቅርስነት እ.ኤ.አ በ1982 በዩኔስኮ ተመለከተ፡፡ በዓለም ላይ ካሉ እጅግ ድንቅ ከተሞች የተመዘገበችው ፍሎረንስ በዓለም አንዷ መሆንዋ የሚበዛባት እንዳልሆነ ተገነዘበ፡፡ ብዙዎቹ የጣሊያን ፀሐፍትና ደራሲያን ለምን ከፍሎረንስ ጋር እንደተያያዙ ገብቶታል፡፡ የወርቃማው ዘመን ፀሐፍት በፍሎረንስ ዘዬ መፃፋቸው እንደ አንድ መስፈርት ይታይ እንደነበር ያነበበውን አስታወሰ፡፡

የማተሚያ መሣሪያ፣ በአሥራ አምስተኛው ክፍለ ዘመን መመስረት በመላው አውሮጳ እንዲቀጣጠል ቤንዚን የሆነው ዳግም ልደት፣ ሁለንተናዊ ነበር፡፡ የእውነታዊነት ስነ-ስዕል ዳግም ልደት፣ የትምህርት ዳግም ልደት፣ የፖለቲካ ዳግም ልደት፣ በኋላ ሳይንሳዊ አብዮትን የቀሰቀሰው የሳይንስ ዳግም ልደት፣ ... በሁሉም ረገድ እንደገና መወለድ፡፡

ኪራኮስ ከዚህ ጋር ኢትዮጵያ ውስጥ ህዳሴ ከሚለው የኢህአዴግ እንቅስቃሴ ጋር አነፃፀረው፡፡ "ግማሽ ተሰርቷ ግማሽ ተላጭታ" የሚለውን ብሂል አስታውሶት ፈገግ አለ፡፡ 'ሁለንተናዊ ያልሆነ ህዳሴ እንደተልባ ስፍር በዚህ ሲቆልሉት፣ በወዲያ የሚናድ ነው' ሲልም ከራሱ ጋር ተነጋገረ፡፡ በ14ኛው ክፍለ ዘመን ፍሎረንስ ውስጥ የተጀመረው የዳግም ልደት እንቅስቃሴ ጥኋቸው ያለፉቸውን አሻራዎች ከፊት ለፊቱ ቃፊርነት የቆሙት ረቂቅና ጥንታዊ ኪነ-ህንፃዎች ተጨባጭና ሁለንተናዊ እንደነበሩ አመለከቱት፡፡ የፍሎረንሱ ዳግም ልደት ምንጭ የሆኑት ጭንቅላቶችን በህሳቡ አስታወሳቸው፡፡ ኮንስታንቲኖፕል በኦቶማን ቱርኮች እጅ በመውደቋ ምክንያት የግሪክ ምሁራን ወደ ኢጣሊያ መሰደድ አንዱ የንቅናቄው ምክንያት እንደነበር አስታወሰ፡፡ በተጨማሪም የመካከለኛው ዘመን ጨለማ ያልበገራቸው የጥበብ ሰዎች እስከ ሥራዎቻቸው በአእምሮው

ውስጥ ውልብ እያሉ ያልፉ ጀመር፡፡ የዘመኑ ሰዓሊያን ብርሃንና ጥላን በመጠቀም ጭብጦቻቸውን ለማስረፅም ሆነ ለመግለፅ የተጠቀሙበት ዘዴ የዳግም ልደቶችን ወርቃማ ጠበብት በሚገማሸረው የእርኖ ወንዝ ላይ ጥላቸውን ሲጥሉ ብርሃናቸውን ሲተክሉ አሳየው፡፡ ምንም እንኳ የዳግም ልደት ዘመኑ ሥነ-ፅሁፍ ትኩረት የሚሰጠው የጥንቶቹን ዘመን እይሻሬ ስራዎች በመተርጎም ላይ ቢሆንም በራሳቸው አዲስ ዘመን ውስጥ አዲስ አሻራቸውን ያስቀመጡትም ደራስያን የቀለጠ ወርቅ በሚመስለው የእርኖ ወንዝ ላይ እያብረቀረቁ በዓይን ህሊናው ታዩት፡፡ እነዳንቴ....፡፡ በዚህም ያለ ጥበብ ዳግም ልደት ሊታሰብ እንደማይቻል ተገነዘበ፡፡

'ይህን ኢትዮጵያ ውስጥ ማድረግ ይቻላል?... ጥበብ ዘመኑን ይፈጥራል? ወይስ ዘመን ጥበበኞችን ይወልዳል?' ሲልም አሰበ-ኪራኮስ፡፡ አባቱ ዕድሜ ልካቸውን የሰበሰቧቸውን የሥነ-ፅሁፍና የምርምር ሥራዎች ሰብስቦ ወደ ኢትዮጵያ ለማስጫን አሰበ፡፡ ሆኖም ይህን ማድረግ እንደማይቻለው ተገነዘበ፡፡ ገና ያልመረመረው እያሌ ምስጢር በአባቱ ቤት ውስጥ እንደሚኖር ሲያስብ በየትኛው ፍጥነት በየትኛው ብጣቂ ጊዜ ሊመረምረው እንደሚችል ሲያስብ ጭንቅ ያዘው፡፡ የዳንቴን ገሀነመእሳት ወደነበረበት የመጻህፍት መደርደሪያ ለመመለስ ከመሄዱ በፊት ሊሊያን አሻግሮ ተመለከታት፡፡ እጅዋን በቀስታ አወዛወዘችለት፡፡ ልቡን የማያውቀው ስሜት ሲገምሰው ተሰማው፡፡ አስተዋላት፣ አስተዋለችው፡፡ ሳያስበው ጣቶቹ መልእክት አስተላለፉበት፡፡ ጣቶቹ ነይ የሚል ምልክት አሳይዋት፡፡ ወዲያውኑ የአፓርታማውን መወራረጃ ይዛ ቁልቁል ስትንደረደር ተመለከታት፡፡ አሳንሰሩን ለመጠቀም እንኳ ጊዜ እንዳልነበራት ተረዳ፡፡ ገሀነመ እሳቱን ወደ መደርደሪያው ሲመልስ፣ አንድ ነገር ትኩረቱን ሳበው፡፡ አንድ አሮጌ ማስታወሻ በመጻህፍቱ መካከል ተወሽቆ ተመለከተ፡፡ ሳበው፡፡ አሮጌውን መዝገብ መዝገቡ በቀይ እራፊ የታሠረ ነው፡፡ አሮጌውን መዝገብ ከአፍንጫውና ከዓይኖቹ ፈቀቅ አርጎ ካራገፈውና የታሰረበትን ቀጭን ቀይ ጨርቅ ከፈታ በኋላ ተጣድፎ ገለጠው፡፡ ቆሎ በመሰለው የአባቱ ቁም ጽሁፍ ተሞልቷል፡፡ እያሌ ገፆች ያሉት ይህ ማህደር ውስጡ ከዚህ ቀደም አይቷቸው በማያውቅ ጠልሰሞችና ምልክቶች የተሞላ ነው፡፡ እስከዛሬ እዚህ መደርደሪያ ላይ ቀርቶ የትም አይቶት የማያውቀው ይህ

ማስታወሻ ከየት እንደመጣ ሊገባው አልቻለም፡፡ አባቱንም ሲያነቡ እንጂ ሲጽፉ አይቷቸው ስለማያውቅ አንዳች የደበቁት ነገር እንደነበር ተገነዘበ፡፡

በዚህ ቅጽበት ሁለት እጆች ከኋላው በቀስታ ሲያቅፉት ተሰማው፡፡

# ፲፫

## አዲስ አበባ

ጌራ ቀይዋን ኮሮላ እንደ ሰንጋ ፈረስ እየኮለኮለ ሚሮዳን ይዟት የሄደውን ጥቁር መኪና ሲከተል ቆየ፡፡ ዝናቡ እየጨከነ በመሆኑ አስፋልቱ ላይ የቆመውን ውሃ ግራና ቀኝ እያፈናጠቀ ለመከታተል አመቺ አልነበረም፡፡ ነጠብጣቡም የፊት መስታወቱን አጥብቆ ስለሸፈነው ግራና ቀኝ እንደሰርገኛ የእስረኛ ምቹውን መንደር፣ ቺቺኒያን ሰንጥቆ ወደ ግራ ታጠፈ፡፡ በእሩራኤል በኩል ሽቅብ ወደ ካዛንቺስ የወጣው መኪና ድንገት ወደ ግራ በመታጠፍ ከዓይኑ ተሰወረበት፡፡

የዝናቡ ነጠብጣብ በመኪናው መጥረጊያ ብቻ የሚገታ አልነበረም፡፡ ሆኖም ቀጭኗን የውስጥ ለውስጥ መሿለኪያ ተከትሎ መንዳቱን ቀጠለ፡፡ ተስፋ በመቁረጥ ስሜት መሪውን ደልቆ መኪናዋን ዳር አስይዞ ወረደ፡፡ ሴቲቷም ተከትላው ወረደች፡፡ የሚያየውን ማመን አቃተው፡፡ አብራው የነበረችው ሴት የነጥብ ሃያ ሁለት ሽጉጧን አፈሙዝ ወደ እሱ ደግና ወደ መኪናው እንዲገባ ምልክት እየሰጠችው ነበር፡፡

"ምን?!" አለ ጌራ ግራ ተጋብቶ፡፡ "እየቀለድሽ ነው?!"

ይህቺ ሴት በድርጅቱ ተመልምላ ቀንጠፋውን እንድታጠምድ የተወከለች እንደነበረች ብቻ ነው የሚያውቀው፡፡ አእምሮው ፈጠነ፡፡ ቆይቶም አንድ ነገር ብልጭ አለለት፡፡ በቀንጠፋው ሰማይና ያስጨመደደቻቸው ይህቺ ሴት እንደ ነበረች ገባው፡፡ ምድሩን ጨምሮ ሁሉም ነገር ቀስ በቀስ እየከዳቸው እንደሆነ ተረዳ፡፡ ሁለት እጆቹን ወደላይ እንዳንከረፈፈ ወደ ጋቢናው ገባ፡፡

ጌራን በዓይነቁራኛ እስገብታ እዷ ከኋላ ወንበር እንደተቀመጠች በጭንቅላቱ ቀጥታ አፈሙዙን ደቀነችበትና መንገዱን እንዲቀጥል አዘዘችው፡፡ ሁኔታውን ለማመን በመቸገር ላይ ቢሆንም፣ በውስጥ መስታወቱ እንቅስቃሴዋን እየተመለከተ ነበር፡፡ ወልፈት ቢል ያለአንዳንች ርህራሄ የሽጉጧን ምላጭ እንደምትስበው አልተጠራጠረም፡፡ ሽጉጡ የራሱ ድርጅት ያስታጠቃት ነው፡፡ ለግድያ እንደሚውል ቢያውቅም እርሱ ላይ ግን ውሃ የሚደፋ እንጂ እሳት የሚተፋ መሆኑን ለማመን ተቸገረ፡፡ 'እነዚህ ሁሉ የዴርቶጋዳ አባላት ይህን ዘግናኝ ክህደት እንዲፈፅሙ ምን ያህል ቢከፈላቸው ነው? ምክንያታቸውስ ምን ይሆን? በቃል የማሉትን መሃላ፣ በደም የገቡትን ቃል-ኪዳን ምን ዋጠው?'ጌራ መብሰልሰሉን ቀጠለ፡፡ወዲያው ግን እነዚህንና የመሳሰሉትን ጥያቄዎች የሚያነሳበት ሳይሆን ጊዜው አሁን የተጋፈጠውን አደጋ ብቻ ለማምለጥ እእምሮውን የሚጠቀምበት እንደሆነ ተገነዘበ፡፡

"ወደ ግራ ታጠፍ!" የሚል ትዕዛዝ ሰጠችው፡፡ ቁልቁል ወደ ቀኝ ያለውን መታጠፊያ ሊጠቀመው ፈለገ፡፡ ሆኖም በውስጥ መስተዋቱ ለቅፅበት የሽጉጧ አፈሙዝ በጭንቅላቱ ቀጥታ ሆኖ እንደተራበ እንበሳ ሲያዛጋ ተመለከተው፡፡ ሽጉጡ ለማስፈራሪያ ብቻ ሳይሆን ለግድያ የተዘጋጀ መሆኑን አላጣውም፡፡ ሆኖም ይህቺ ሴት ጌራን ያህል የዴርቶጋዳ አባል የመግደል ስልጣን አይኖራትም ሲል አሰበ፡፡ ምናልባት ስልጣኗ አቁስሎ ይዞ እስከማስረከብ ይሆናል የሚል እምነት አደረበት፡፡ ነገር ግን ሌላም ሀሳብ ብልጭ አለለት፡፡ ይኸኔ ከኋላዋ አንድ ፓትሮል ሙሉ ኃይል እየጋለበ ይሆናል ሲል አሰበ፡፡ ይህ ሃሳቡም ትክክል ለመሆን አልተጠራጠረም፡፡ ሁኔታዎች እየጠጠሩ ከመምጣታቸው በፊት ራሱን ማዳን እንዳለበት ወሰነ፡፡

ከመኪናው መሳቢያ ውስጥ ያለው ሽጉጡ የዕንፈ ዓለምን ያህል ራቀው፡፡ መሳቢያው በእርግጥ አልተቆለፈም፡፡ የጣት ማስገቢያ ያህል ገርበብ ብሏል፡፡ በምን ፍጥነት ይህን ማድረግ እንዳለበት ሲያስበው የህልም ሩጫ ሆነበት፡፡ በእጁ እና በመሳቢያው መሃል ያለው አንድ ክንድ ርቀት የእድማስ ማዶን ያህል ረዘመበት፡፡ ሆኖም በቅፅበት አንድ ሀሳብ መጣለት፡፡ የመኪናዋን ሞተር

ለወጠችው፡፡ ጥቂት ቆይቶ ደግሞ ብርቱን ወደ ጨለማነት ለወጠችው፡፡ ጥቂት ቆይቶ ደግሞ ብርሃን ወደ ጨለማነት ሲያርፍ ተሰማው፡፡ በአገኛት አንዳች ፍንጣሪ ማጅራቱ ላይ ሲያርፍ ተሰማው፡፡ በአገኛት አንዳች ፍንጣሪ ቁልቁል ለመሮጥ ወሰነ፡፡ ነገር ግን እንዴት ወባብ መታጠፊያ ቁልቁል ለመሮጥ ወሰነ፡፡ ነገር ግን እንዴት ወባብ መታጠፊያ ባለማወቁ፡ ጥቂት ቆሞ ሲያመነታ መንገዱ የት እንደምታደርስ ባለማወቁ፡ ጥቂት ቆሞ ሲያመነታ መንገዱ የት እንደምታደርስ ለጥቂት አለፈው፡፡

ከኋላው የሚያፏጭ ጥይት ለጥቂት አለፈው፡፡

መንገድ በመሸከሉክ ከጥይት ነፍስ አውጭኝ በማለት በጠባቧ መንገድ በመሸከሉክ ከጥይት ነፍስ አውጭኝ በማለት በጠባቧ እየሮጠ ሳለ የግራ እግሩ ሽብረክ ኢሳግ ላለመግባት በትዝምዝም እየሮጠ ሳለ የግራ እግሩ ሽብረክ ኢሳግ ላለመግባት በትዝምዝም ሁለት እጆቹ ወደ ሲል ታወቀው፡፡ ወገቡ ወደኋላ ታጠፈበት፡፡ ሁለት እጆቹ ወደ ሲል ታወቀው፡፡ ወገቡ ወደኋላ ታጠፈበት፡፡ ሚዛኑን መጠበቅ አቅቶት ወደ ግራ ላይ ተንጨፈረሩበት፡፡ ሚዛኑን መጠበቅ አቅቶት ወደ ግራ ላይ ተንጨፈረሩበት፡፡ ወዲያው ደግሞ ወደቀኝ ተንጋደደ፡፡ የጁጋን ቅርፅ ሠራ፡፡ ወዲያው ደግሞ ወደቀኝ ተንጋደደ፡፡ የጁጋን ቅርፅ ሠራ፡፡ የቆመበትን ተመለከተ፡፡ የተጨራረፉ እንደምንም ታግሎ የቆመበትን ተመለከተ፡፡ የተጨራረፉ እንደምንም ታግሎ መንገድ ከሚንጮለጮለው የጠራ የብርሃን ጨረሮች ባረፉበት መንገድ ከሚንጮለጮለው የጠራ የብርሃን ጨረሮች ባረፉበት የሰራ ነገር ተመለከተ፡፡ ደሙ ጎርፍ ላይ አለላ የመሰለ መስመር የሰራ ነገር ተመለከተ፡፡ ደሙ ጎርፍ ላይ አለላ የመሰለ መስመር እግሩ መመታቱን አወቀ፡፡ ህልም መሆኑን ተገነዘበ፡፡ ግራ እግሩ መመታቱን አወቀ፡፡ ህልም መሆኑን ተገነዘበ፡፡ ግራ መሰለው፡፡

'ለመሆኑ ይህ ህልም ነው ወይንስ እውን? ይህ ቅዠት መሆን አለበት!'

"ቁም!" የሚል ድምፅ ተሰማው፡፡ ሁለት ሜትር ያህል ራቅ ብሎ ከተጭኗ መንገድ ጠርዝ የቆየ የግንብ አጥር ተመለከተ፡፡ ወደቀኝ የምትዘልቅ መታጠፊያ እንዳለችም ተረዳ፡፡ እንደምንም ተፍገምግሞ ወደ መታጠፊያዋ ደርሶ በመጠለል ራሱን ለመከላከል ድምጥማጡን አጠፋ፡፡

ሕይወታቸውን ሁሉ ለጥተውለት ለነበረ ድርጅት አብራው ትሰራ የነበረች ባልደረባው እንዴት ዛሬ ከመቅፅበት ተገልብጣ ልትገለው የጥይት እሩምታ ታወርድበታለች? ለዚህ የሚያበቃ ይኼ ነው የሚባል አመርቂ ምክንያትስ እንዴት ልታገኝ ቻለች? አሁንም እያስከለከ የሚያሰበው ይህንኑ ነው፡፡

'እም! ልትገለኝ ቆርጣለች!... ይህ እንዴት ሊሆን ይችላል?! ...የለም! ... አይሆንም! ይህ ቅዠት መሆን አለበት!'

ጆንስ ሱሪው ከታች ተቦትርፏል፡፡ ያደረገው የግራ እግሩ ነጭ ሰኒከር ጫማ ቀልቷል፡፡ ውስጡ ይሞቀዋል፡፡ የሚያስርበት ጊዜ አላገኘም፡፡ ቁልቁል በሚወርደው ጎርፍ ላይ እግሩን እያንቦጫረቀ የሚወርድ ኮቴ ተሰማው፡፡ ሽጉጡን ጠበቅ አርጎ

ያዘ፡፡ ኮቴው እየቀረበ መጣ፡፡ ቡጭ! ቡጭ! ዱሌፈስ! ዱሌፈስ! ጨቅ! ጨቅ! ጨቅ!.... ከዚሁም ጋር እልፎ እልፎ የሚያቃስት ድምጽ..... እየቀረበችው እንደሆነ አወቀ፡፡ ታግተመትማለች፡፡ ምን እንደምትል ግን አትሰማውም፡፡ ትንፋሽዋ ሳይቀር እየቀረበው ሲመጣ ታወቀው፡፡ ጫን ጫን ትተንፍሳለች፡፡ ታለከልካለች፡፡ ቅድም የመታት የእጁ ቁስል መሆን አለበት፡፡ ወዲያው ፀጥታ ሆነ፡፡

'የሄድኩበት ጠፍቷት መሆን አለበት' ሲል አሰበ ጌራ፡፡ ነገር ግን ደሙን ተከትላ እንደምትመጣ ሲገለጽለት በተጠንቀቅ ትንፋሹን አጥፍቶ በመቆም መጠባበቁን ቀጠለ፡፡ ወዲያው ግን በሁለት ህሳቦች መሃል እንደቆዳ ተወጠረ፡፡

'ልግደላት? ወይስ አቁስዬ ልመርምራት? በዚህ መሃል ከኋላዋ የቧ ጎይሎች ቢደርሱብኝስ?' እያለ ሲያምሰለስል ከፊት ለፊቱ ጥላዋ ዘው ሲል ታየው፡፡ እንደ እንሽላሊት ከአጥሩ ጋር ተሳጥቆ ትንፋሹን ያዘ፡፡ ከኋላዋ በኩል በዛፎቹ ቅርንጫፎች ውስጥ የመጡት የመብራት ጨረሮች ከእርሷ ኋላ ሆነው እሱ የተጠለለበት ጥግ ግን ጨለማ ባይሆን ኖሮ ትቀድመው እንደነበር ተረድቷል፡፡ ላፍታ ጎንበስ ብላ ጎርፉን ተመለከተች፡፡ ከእርሱ የምትርቀው ሁለት ክንድ ብቻ ነው፡፡ በመካከላቸው የሚወርዱት የዝናቡ ነጠብጣቦች ብቻ ናቸው፡፡ ቁልቁል እያቃሰተች ዝቅ ብላ ደሙን በመመልከት በዛ እልፎ ይሁን አይሁን አጠናች፡፡ በደሙ ስትከተለው እንደቆየች አረጋገጠ፡፡ ከእግሩ የሚንጠለጠለው ደም ከፊቷ የሚንጮለጮለውን ጎርፍ እያቋረጠው መሆኑን ሲያይ ደነዘዘ፡፡

ዘሎ ሊያንቃት ከጀለው፡፡ በአንዲት ጥይት ሀቅ ሊያረጋትም አሰበ፡፡ ነገር ግን በመጀመሪያው ሀሳቡ ፀና፡፡ ተጎንብሳ ደሙን ስታይ ዘሎ ተከመረባት፡፡

ጎርፉ ላይ ይተናነቁ ጀመር፡፡ የሁለቱም ሽጉጦች ግራና ቀኝ ተበታተኑ፡፡ የሁለቱም እጆች ወደ ሽጉጦቹ ተንጠራሩ፡፡ ጣቶቻቸው እንደጦር ሹለው እንደ እንቴና ይመዘዙ ይመስል ተገተሩ፡፡ ጌራ ሽጉጡን እንዳትይዝ ለመከልከል እንጂ ሽጉጡን ለመጠቀም አላሰበም፡፡ ጥይቶቹን መጨረስ አልፈለገም፡፡ የፍልሚያው አሸናፊ ከሆነም የእርሷንም ሽጉጥ ለመጠቀም አስቧል፡፡ ቦርሳዋን እስካሁን ስላልጣለችው በቦርሳዋ ውስጥም

እንደማያቅማሙ በማወቁ ይህን ማድረጓ አላስደነቀውም፤ የቄስ ጥምጣም ሸብ አድርገው ቤተ መቅደስ ጥልቅ የሚሉ እንዳሉም ያውቃል፡፡

ቋሰለኛ እግሩን ቦርሳው ውስጥ ባገኘው ሻርፕ ግጥም አርጎ ካሰረ በኋላ በዝናብ የበሰበሰ ልብሱን አወላልቆ አባያና ኒቃኑን ከራስ ጠጉሩ እስከ እግር ጥፍሩ አጥልቆ እያጠለቀሰ ከአካባቢው ተሰወረ፡፡ ልብሱ ለጊዜው ከሚከታተሉት ሰዎች እይታ እንደሚሰውረው ገምቷል፡፡

"ከእንግዲህ ከአንድ ኮልት ሽጉጥና ከአንድ ኮት በቀር ጓደኛ እንደሌለኝ አረጋግጫለሁ፡፡" ነበር ያለው ኮቱንና ኮልቱን የከተተበትን የሴት ቦርሳ ወደ ትክሻው እየገፋ፡፡

# ፲፬

ሚራዥ ረጅሙን ኮሪደር አቋርጦ ወደ ሻጊዝ ቢሮ ገባ፡፡ ሻጊዝ ካፈጠጠበት የኮምፒዩተር ገፅ ላይ ዓይኖቹን አንስቶ ሚራዥን ይቀመጥ ዘንድ፣ ከፊት ለፊቱ ያለውን ወንበር ጋበዘው፡፡

ለደቂቃዎች ሁለቱም ዝም ብለው ሲጠባበቁ ከቆዩ በኋላ ሚራዥ ያቀባበለውን ጥያቄ ተኮሰበት፡፡

"ሁለገብ ትግል እያልክ ትሰብክ አልነበረም እንዴ? እረ ለመሆኑ ያን የሚንተገተግ ስሜትህን ምን በላው?" ሚራዥ ጠረጴዛ ጠረጴዛውን እየተመለከተ የሻጊዝን ዓይኖች ሳያይ በጥያቄ ያጣድፈው ጀመር፡፡

"እረ ለመሆኑ ሁለገብ ትግል ስትል ምን ማለትህ ነበር? ከኢህአዴግ አባላት ሱቅ ሲጋራ አትግዙ ማለት በቂ ይመስልሃል? እንዴት በዚህ አጣብቂኝ ጊዜ ዝም ትላለህ? ጠላቶቻችን እሰፍሰፈው እጆቻችንን ሊይዙ በሚገሰግሱበት ሰዓት እንዴት ዝም ትላለህ?"

"ወንድም ሚራዥ ልብ ብለህ አዳምጠኝ፡፡ ጦርነት ከምድር ተነስቶ አይጀመርም፡፡ ሁሉም ነገር አቅምን አውቆ ሲደረግ ነው መልካም፡፡" ሻጊዝ ጠረጴዛው ላይ ዓይኖቹን ልክ እንደሚራዥ ተክሎ መለሰለት፡፡

"ምን ማለትህ ነው?" ሚራዥ ዓይኖቹን ከሻጊዝ ዓይኖች ላይ ተክሎ ጠየቀው፡፡ ሻጊዝ ሻጊዝ አልመሰልህ አለው፡፡ ምናልባት ሎስ አላሞስ ውስጥ የጓክ ዶናልድ ሲሞን ፊት ተቀይሮለት ጓክ ዶናልድ ሲሞን ከተባለ በኋላ የመጣበት ለውጥ ይሆናል ሲልም ገመተ፡፡ ምናልባት የፊቱ መቀየር አንዳች ሥነ-ልባናዊ ተፅዕኖ ይኖረው ይሆን? ሲልም አሰበ፡፡ ወኔው፣ ለዛው፣ እውቀቱ፣ አመለካከቱ ሁሉ እሱን እሱን አልመሰልህ አለው፡፡

"ምን ማለቴ መሰለህ ..." አለው ሻጊዝ ወይም ጓክ ዶናልድ ሲሞን፡፡ "ጦርነት ከመጀመርህ በፊት ማሟላት ያለብህ ብዙ ቅድመ ሁኔታዎች አሉ፡፡ በቂ የሰለጠነ ኃይል አለኝ? በቂ ስንቅ አለኝ?

የዲፕሎማሲ ድጋፍ አለኝን? የአካባቢው ማህበረሰብ ድጋፍ አለኝን? ጦርነት ስለምንዋጋው የጠላት ወገን ወታደራዊ አቅምና አቋም የሚመልስ ሁለገብ መረጃ አለኝን? ከዚህም በተጨማሪ አቅም ከጠላት የተሻለ መሣሪያ አለኝን?... ብለህ ማሰብ በመጀመሪያ ከዚህም ሌላ መዘንጋት የሌለባቸው አያሌ ጉዳዮች አሉ፡፡ ማፈግፈጊያ ሀገር አለኝን? ብለህ ማሰብም ግድ ይላል፡፡ ያለነው አመሀል ሀገር ነው፡፡ አይደለምን ከጣና ሐይቅ ብዙም ባልራቀ ሁኔታ በአዲስ ዘመን ተራሮች ውስጥ ነን ያለነው፡፡ የጠላት ኃይል ቢያይል ወደየት እናፈገፍጋለን? በየትኛው ብሄር መሬት ላይ ወታደራዊ ልምምድ ለአዲስ ምልምሎች እንሰጣለን? ወይ ሱዳን ጠረፍ አይደለን ወደ ሱዳን እናፈገፍግ! ወይ በኬንያ አዋሳኝ በኩል ወይንም በሶማሊያ ድንበር አይደለን ወደ ጎረቤት ሀገር እናፈገፍግ! ይህ ቦታ ሳይኖረን ጦርነቱን መጀመር ምን ይባላል? ይህም ብቻ አይደለም፡፡ ከጦርነቱ የምናገኘው ትርፍና ኪሳራ በደንብ ተሰልቷል?" ሻጊዝም በበኩሉ ማራኝን አፋጠጠው፡፡

"ያነሳሃቸው ጥያቄዎች ሁሉ መሠረታዊ ናቸው፡፡" አለ ማራኝ ወደ ጥናው ነጥብ መቃረባቸውን በማመን፡፡ "ጦርነት ማለትም እነዚህን መሠረታዊ ጥያቄዎች ከመመለስ ይጀምራል፡፡ በቂ የሰለጠነ ኃይል አለን ወይ? ላልከው መልሴ በቂ የማለው ቃል አሻሚ በመሆኑ መመለሱ ከባድ ነው፡፡ በቂ የሰለጠነ ኃይል ማለት በጠላት ሠራዊት ልክ ቁጥር ያለው እኩል ሠራዊት ማሰለፍ አለመሆኑን ግን ያስገነዝበኛል፡፡ የእኔ ሠራዊት የጠላትን ሠራዊት በቁጥር ያንሳል ተብሎ ጦርነት አይሰረዝም፡፡ በቂ ስንቅ አለን? ላልከው ... በቂ ስንቅ የለንም፡፡ እንዲያውም ተራራው ውስጥ ያለው ቀለብ ሁሉ እየተሟጠጠ ነው፡፡ ከተራራው ውጭ ካለው ህዝባችን ጋር ያለው ሰንሰለት ስለተበጠሰ ወደዚህ ተራራ ቀለብ መምጣቱ ቆሟል፡፡ ከጥቂት ቀናት በኋላ የምንልሰው የምንቀምሰው አይኖረንም፡፡ ይህም ለጦርነቱ አንዱ ምክንያት ነው፡፡ ይህ Survival war ነው- የሞት ሽረት ትግል፡፡ አንተ እምቢ ብለህ ማንም ሊታስቆም የማትችልበት አንዱ ምክንያት ይኸው ነው፡፡ 'ከረሃብ ጦርነት ይሻላል' የሚለው ጥንታዊ ብሂል እውነትነት አለው፡፡

"የመልክአ ምድር ድጋፍ አለን? ላልከው-ከእነሱ የተሻለ እኛ የመልክአ ምድር ድጋፍ አለን፡፡ ቅድሚያ የሚፋለሙት ከአዲስ ዘመን ተራሮች ጋር ነው፡፡ የአካባቢው ማህበረሰብ ድጋፍ

አለን ወይ? ላልከው በዚህ በኩል የተሠራ እንዳችም ሥራ የለም፡፡ ይህ እውነት ነው፡፡ እንደኛ እኛ ሽምቅ ተዋጊዎች ሳንሆን ምሁራዊ ማህበረሰቦች ስለሆንን የአካባቢው ማህበረሰብ እኛን እንዲያውቀን እንፈቅድለትም፡፡ በድብቅ ለስንት ዘመናት የኖርን ማህበረሰቦች እንደሆንን ታውቃለህ፡፡

ጦርነት ስለምንገጥመው የጠላት ጦር መረጃ አለን ወይ? ላልከው፣ በመጠኑ አለን፡፡ ኮ/ል አሲጋዝ ቂርስ ከዚህ ተራራ ውጭ በመሆን አንዳንድ ጉዳዮችን እንዲያጠና ነግሬው ደፋ ቀና በማለት ላይ ነው፡፡ ፀጠሩ አባል በመሆኑ በድብቅ ብዙ መረጃዎችን በመሰብሰብ ላይ ነው፡፡ የጠላትን አቅምና ቁጥር እንዲሁም ትጥቅ ለማወቅ ጥረት በማድረግ ላይ ነው፡፡ በቅርብ ጊዜም መረጃውን ያደርሰናል፡፡

ማፈግፈጊያ ሀገር አለን ወይ? ላልከው የለንም፡፡ እኛም እናፈገፍግም፡፡ የማፈግፈግ ዓላማ የለንም፡፡ በዚህ ዘመን የማፈግፈጊያ ሀገር ተይዞ ጦርነትን ማሸነፍ አይቻልም፡፡ የአፍሪካ መሪዎች በሙሉ በአንድ ቢላዋ የሚመተሩ፣ በአንድ መንጋጋ የሚፈጩ ከሆኑ ቆይተዋል፡፡ ስለዚህም የትኛውም ሀገር ማፈግፈጊያ ሳይሆን ሚሆነን፣ ማፈኛ ነው፡፡ እዚሁ ሀገራችን ውስጥ እንፋለማለን፡፡ እንሞታለን፡፡ እንቆስላለን፡፡ አፈርን ልሰን እንደገና እንሞክራለን፡፡ ይህን ስል ግን ዓላማችን ግልጽ ነው፡፡ የጦርነቱ ትርፍ ምንድን ነው? ላልከው፣ እኛ መጀመሪያም ጦርነቱን አልፈለግነውም፡፡ መጀመሪያም የከበቡን ራሳቸው ናቸው፡፡ የጦርነቱን ትርፍ የሚያውቁት እነሱው ናቸው፡፡ በእኛ በኩል የመጀመሪያ ዓላማችን በዚህ ተራራ ክርሰ ምድር ውስጥ ያሉትንና ከሁለት ሺህ ስምንት መቶ በላይ የሆኑ ጭንቅላቶችና የቃል-ኪዳን ልጆች ማዳን ነው፡፡ የሚድኑትም በራሳቸው እንጂ በሌላ በማንም አይደለም፡፡ በምዕራባውያን ወይም በምስራቃውያን ድጋፍ መዳን የሚሻ የለም፡፡ ሁሉም የራሱን ጦርነት ለራሱ ነፃነት ያረገዋል፡፡ በድጋፍ የመጣ በንፍገት ይመለሳል፡፡ ይህ ውጊያ ያለድጋፍና ያለማፈግፈጊያ የምናደርገው ውጊያ ነው፡፡ የጦርነቱ ትርፍ ይኸው ነው፡፡ ኪሳራውስ ተሰልቷል? ላልከው፣ በደንብ ተሰልቷል፡፡ ምናልባት ትልቁ ኪሳራ የሰው ህይወት ነው፡፡ እሱን እንከስራለን፡፡ ህልምን ከመክሰር ህይወትን መክሰር ይሻላል፡፡ ያለህልም ህይወት በራሱ ኪሳራ ነው፡፡" ግራኝ ይህን ሁሉ ብሎት ሲያበቃ ፈገግ አለ፡፡

በሁለቱ መሀል የተደረገ መሠረታዊ ውይይት እንደሆነም ተገነዘበ፡፡ ለረጅም ጊዜ ግልጽ ባልሆነ ሁኔታ ዓይኖቻቸው ሳይላቀቁ ቆዩ፡፡

ሚራዥ ከዚህ በላይ መቆየትም መናገርም አልፈለገም፡፡ ተነስቶ እየወጣ እያለ ገና ዶናልድ ሲሞን ወይም ሻጊዝ አንድ ጥያቄ ከጀርባው አስከተለበት፡፡

"ምናልባት ሁላችንም ብንሞትስ?"

"የዶሮቶጋዲ ህልም ሥጋ ለብሶ ስላልሆነ፤ አይሞትም፡፡"

# ፲፭

## ፍሎረንስ + ኢጣሊያ

ከኋላው ያቀፉት እጆች የሊሊያ መሆናቸውን ባንኖ ወደኋላው ሲዞር ተመለከተ፡፡ በኃይል ስባ አቅፋ ወደ ደረቷ አስጠጋችው፡፡

"ምን እንደ ሴት ያሽኮረምምሃል… የኔ ደደብ….. ቢያንስ ለሀዘንህ መርሻ አልሆንህም እንዴ?….ደ'ሞ ፈሪ ሆንህ ነው እንጂ ትወደኛለህ…." እንዲናገር እድል ሳትሰጠው ወደ ባኞ ቤት እየጎተተች ወሰደችው፡፡

ዞማ ፀጉሯን ከግራ ወደ ቀኝ እወናጭፋ ከተቀመጠችበት ተነሳች፡፡ የነጭ ሸሚዙን ቁልፎች መፍታት ጀመረች፡፡ ኪራኮስ ሊሊያን አሻግሮ ሳይሆን ቀርቦ ሲያያት ቆንጆናዋ ጎላበት፡፡ ዓይን የማያስነቅሉ ዓይኖቿንና የበሰለ የሎምጫ ፍሬ የመሰሉ ከንፈሮቿን አፈራርቆ ተመለከታቸው፡፡ በቆመበት ሰቃው ጉድጉድ ትል ጀመር፡፡ የምታረገውን ቆሞ ከመመልከት በቀር ምርጫ አልነበረውም፡፡

ሊሊያ ለብ ባለ ውሃ ገንዳውን ሞልታ ከገባች በኋላ የኪራኮስን እጅ ስባ ገንዳው ውስጥ እንዲገባ ጋበዘችው፡፡ ኪራኮስ ለብ ባለ ውሃ ወደተሞላው ገንዳ ከገባ በኋላ ከእርሷ ተቃራኒ ያለውን ጥግ ይዞ ተቀመጠ፡፡ በውሃው ውስጥ አካሏ ይታይ ነበር፡፡ ጥርት ያለው ገለዋ ለወጣትነቷ ቃፊር ቆሟል፡፡ ጡቶቿ ገና እንደተቀሰሩ ናቸው፡፡ በአካሏ ውስጥ የሚራወጠው ደሟም ድንገት መንገድ ስቶ ከቆዳዋ ውጭ የሚፈስ መሰለው፡፡

ሊሊያ የሞቁ የፍቅር ምልክቶችን ታሳየው እንደነበር ያስታውሳል፡፡ ምልክቶችን እንዳላየ ሲያልፍ ነበር፡፡ ግን ያ ሁሉ የእውነተኛ ፍቅር ምልክት ይሁን ወይስ በእርሷ በኩል በተዘረጋ አሽከላ ውስጥ ለመክተት የተቀየሰ ወጥመድ? ሊገለዕለት አልቻለም፡፡

በሞቀው ውሃ ውስጥ ቢሆንም፣ እፁ ወጥመዱ ትሁን ወይስ ወዳጁ የሚለውን ሲያሰላስል ሰሚቱ ሲንቃቃለት አልቻለም፡፡ ቢሆንም ይሁን አልያ ለመጣችበት ማንኛውም ተግባር ብታውለው ከዚህ ቀጥሎ የሚያደርገው ጉዳይ ግድ አልሰጠውም፡፡ የምርንም ከሴቶች ጋር መውጣት ካቆመ ብዙ ጊዜ እንዳለፈው ተገነዘበ፡፡ እንዲያውም ሰሚቱን በጥቂቱ ያነቃቃለት ዘንድ ውስኪ ነገር ለማምጣት ከገንዳው ወጥቶ ወደ ሳሎኑ ሄደ፡፡ ከጥቂት ደቂቃዎች ቆይታ በኋላ ጠርሙስ ሙሉ የስኮትላንድ ውስኪ ከሁለት ብርጭቆዎች ጋር ይዞ ተመለሰ፡፡ ውስኪውን ሊሊያ ትክፍት ዘንድ ጋበዛት፡፡

"ግሩም ውስኪ ነው!" ስትል ከቀመሰችው በኋላ አድናቆቷን ገለፀችለት፡፡

"ስኮትላንዶችን በውስኪ ጠመቃ የሚችላቸው የለም፡፡"

"እርግጥነው!" ስትል እንደገና መለሰችለት ብርጭቆቻቸውን ሲያጋጩ፡፡

"ይኸኛው ውስኪያቸው አባቴን ያስታውሰኛል ይገርምሻል፡፡ ያዘወትረው ነበር፡፡" ኪራኮስ አባቱን ሲያስብ አንገቱን አቀረቀረ፡፡

ሊሊያም ሀዘኑን ተጋራችው፡፡ እግሮቹ በሞቀው ውሃ ውስጥ ከሊሊያ እግሮች ጋር ሲነካኩ ፊጥኖ ወደ ራሱ መለሳቸው፡፡ ሊሊያ ግን እግሮቹን በእግሮቿ ተከትላ ደረሰችባቸው፡፡ ጣቶቹን በእግሮቿ ጣቶች ነካካቻቸው፡፡ ደቂቃዎች በዝምታ ነጎዱ፡፡

ኪራኮስ ሀሳብ ወሰድ መለስ እያደረገው ከውስኪውም እየተጎነጨ ከቆየ በኋላ ሰውነቱ በመጠኑ ይፍታታለት ጀመር፡፡ ሊሊያ ዓይኖቿን አትዝዛ የኪራኮስ ዓይኖች ላይ እንደተከለች እሱ ወደተጠጋበት የገንዳው ጥግ የሞቀውን ውሃ እምቦጫረቃ ተጠጋችው፡፡ እጆቿን በውሃው ውስጥ ሰዳ በጣቶቿ የደረቱን ፀጉር ታተረማምስ ጀመር፡፡ ይባስ ብላ በጭኖቹ መሃል ግብታ ጡቶቿ ደረቱን ቀስፈው እስኪይዙት ወጣችበት፡፡ ከዚህ ቀጥሎ ያለው ተግባር የእርሱ መሆኑን እስኪገነዘብ ጋለበችው፡፡ ኪራኮስም ይህን አላጣውም፡፡ ከደቂቃዎች ፍልሚያ በኋላ ጨዋኸቷን ትለቀው ጀመር፡፡ ስታቃስት ደንታ አልነበራትም፡፡

ፍልሚያውን ሁለቱም አሸናፊዎች አልነበሩም፡፡ ሲሊያ ከፍቅረ የተነሳም ይሁን ወይ ልማዷ በመሆኑ ፈጥና ተወናቀቀች፡፡ ኪራኮስ ግን ውጥረት ላይ ስለሆነ አእምሮው በመሀል በመሀል ከፍልሚያው ውጭ እየሄደ ይመለስ ስለነበር ለመጠናቀቅ ዘገየ፡፡ ተለቃልቀው ከገንዳው ከወጡ በኋላ ወደ ሳሎን ሄደው ልብሳቸውን ለባበሱ፡፡

"እንደው ትንሽ ምግብ ብቀቅልልህ ምን ይመስልሃል? ይኸኔ ሳትበላ ይሆናል ውስኪውን እየጠጣህ ያለኸው ..." ስትል ወደ ኩሽናው እየሄደች ጠየቀችው፡፡ "አይዞህ ከፈረንሳዮች ባልሻልም ምግብ ቅቀላ ላይ አልታማም፡፡"

"ካልሽስ ለምኑን ምግቡም አልተበላኝ፡፡"

"ግዴለህም የኔን ትወደዋለህ፡፡" አለች ሊሊያ ወደኋላዋ ዙራ ፈገግ ካለች በኋላ፡፡ "እስከዛ ድረስ ግን የምትሰራው ሥራ ካለ ስራ፡፡"

የሊሊያ ምግብ እንዳለችውም ጣፋጭ ነበር፡፡ ተመግበው ሲያበቁ ሊሊያን ከሸኘ በኋላ የጓጓለትን ያባቱን ማህደር ያገላብጥ ጀመር፡፡

# ፲፯

## ሱሉልታ

ጎህ ሊቀድ ተቃርቧል፡፡ ጥቅጥቅ ያለ ደን የሞሸራቸው ተራሮች ጎፈራቸውን ከፍክፈው ታዩት፡፡ ወደ ምሥራቅ በኩል የሰማዩ ወርቄ ፈገግ ብሏል፡፡ የክረምቱ ወራት ማየሉን ያወቀው፡ አዲስ አበባን ሌቱ እንኳ ዝናቡ ስላልለቀቀው ነበር፡፡ እንደ ሌሊቱ ባይበረታም እንደ አልቃሻ ልጅ እኝኝ ማለቱን አላቆመም፡፡ በተራራዎቹ ጎፈሬ ላይም ስስ ጉም ሸው እያለ ያልፍ ነበር፡፡

ጉራ መንገዱን አልወደደውም፡፡ ሱሉልታ ሊደርስ ጥቂት ርቀት ሲቀረውም ማንም እንዲያየው አልወደደም፡፡ ፍጥነቱን ለመጨመር ሞከረ፡፡ ነገር ግን ከድካሙ ብዛት የተነሳ ጡንቻዎቹ በመዛላቸው እግሮቹን እንኳ መንቀል ተስኖቷል፡፡ የቆሰለ እግሩን እየጎተተ ሲሄድ ያደረው ሱሉልታ የመድረስ ሕልም ስለነበረው ነበር፡፡

እውንም ሳለመበገር ቆረጠ፡፡ ከሱሉልታ በስተምሥራቅ የደን ጎፈራቸውን ባበጠሩት ተራሮች ላይ የሚወነጨፈውን ጉም ይሰፈር ይመስል፡ ለጥቂት ደቂቃዎች ፈዞ በመመልከቱ ተገርሟል፡፡ የቀሩት ጥቂት ኪሎ ሜትሮች ለዘላለም ቢጓዝ እንኳ የማይፈጁት አልመሰልህ አለው፡፡

‘አይቀ ወልዳ ወልዳ ከጅራቷ ሲደርስ ሲጥ’ የሚለውን ተረት ለራሱ ተረተ፡፡ ‘ምንጊዜም ጥቂት ሲቀረን እንደከማለን፡፡’ ሲል አሰበ፡፡ ተረቱን ቢተርትም በቃላት ቢቃትትም ድካሙ በዚህ የሚለቀቀው አልሆነም፡፡ ከዋናው መንገድ ወጣ ብላ ወደ ቆመች ዛፍ ሄደና እርሷን ተገን አድርጎ አረፈ፡፡ ለጉዞው የመኪና መንገዱን የተጠቀመው አልፎ አልፎ ነበር፡፡ ታክሲ ተከናትሮ ከአዲስ አበባ ከተማ ከወጣና አቀበቱን ከጨረሰ በኋላ በድንገት

ታክሲውን አስቁሞ ወርዶ በየጥሻውና በየጉራንጉሩ እያቆራረጠ፣ እቋራጭ በሌለውም የመኪና መንገዱን ዳር ይዞ እየተጓዘ ነበር ሲሄድ ያደረው፡፡ ታክሲው እንዳይጠራጠረው ከግል ከህሎቱ በተጨማሪ ተራራው ውስጥ ዕያለ የሰለጠነው የማስመሰል ስልጠና ሳይጠቅመው አልቀረም፡፡ አዲስ አበባ ውስጥ መታከም እንደማይችል በማወቁ ብቻም ሳይሆን ሱሉልታ የሚገኘውን የዴርቶጋዳ ህዋስ ለመቀላቀልም ነበር የጉዞው አላማ፡፡ ሱሉልታ ውስጥ በሚገኝ አንድ ግቢ ውስጥ የትኛውንም ትዕዛዝ ከኔራ ለመቀበል ተዘጋጅቶ አንድ ቡድን እንደሚጠባበቅ ያውቃል፡፡ ወደዚህ ቡድን ስልክ መደወል ይችል ነበር፡፡ ነገር ግን ሌሊት ላይ ያደረገው ፍልሚያ ተንቀሳቃሽ ስልኩን ከጥቅም ውጭ አድርጎበታል፡፡ ዝናቡም ድምጥማጡን አጥፍቶበታል፡፡

ወደ ሱቅ ጎራ ብሎ እንዳይደውልም ያጋልጠኛል ሲል ሰግቷል፡፡ የመንገድ ስልኮችንም ለመጠቀም ከጅሎ ነበር፡፡ ሆኖም ማንኛውም የዴርቶጋዳ አባል ከሚታወቁ ስልኮች በቀር አያነሳም፡፡ ደዋይም ከራሱ ስልክ ውጪ በሌላ ስልክ አይደውልም፡፡ ስለዚህ ኔራ በየትኛውም ስልክ ቢደውል ማንም እንደማያነሳለት አስቀድሞ ያውቅ ነበር፡፡ ይህም ባይሆን ኖሮ ወደ ሱሉልታ መጓዙ አይቀሬ ነበር፡፡

የታገቶችውን ሜሮዳን ብቻውን ማስለቀቅ እንደማይችል ያውቀዋል፡፡ በግሉ እንዲህ ዓይነት የጀብደኝነት ድርጊት መፈፀም እንዳይችል የድርጅቱ ደንብ ያግደዋል፡፡ በድርጅቱ ደንብ መሠረት የትኛውም ኦፕሬሽን ከመከወኑ በፊት በድርጅቱ ማዕከላዊ ህዋስ ተጠንቶ መፅደቅ አለበት፡፡

ኔራ ጥቂት እረፍት ካደረገ በኋላ በግድ ለመነሳት ሞከረ፡፡ ገና እንደተወለደ እንቦሳ በግድ ተውተርትሮ ቆመ፡፡ መራመድ ህልም ሆነበት፡፡

'ባላረፍኩ ይሻለኝ ነበር' ሲል ራሱን ወቀሰ፡፡ ደሙ የረጋ መሰለው፡፡ ወባ እንደያዘውም ይንቀጠቀጥ ጀመር፡፡ ብዙ ደም ስለፈሰሰው እንጂ ቁስሉ እንኳ ይህን ያህል ለከፉ አይሰጥም ነበር፡፡ ጥይቱ ያገኘው ባቱን እንጂ አጥንቱን እንዳልሆነ የተገነዘበው ጉዞ ከጀመረ በኋላ ነበር፡፡

እንቧትሮ ጥቂት ከቆመ በኋላ በግድ የግራ እግሩን ነቅሎ የቀኙን አስከተለ፡፡ በመኪና እሳፈራለሁ ቢል ተከታዩን ተገንዝቦታል፡፡ የለበሰውን ኒቃንና አበያውን በትጡ ለሳር እንኳ እርግጠኛ አይደለም፡፡ ከሩቅ ሴት ያስመሰለው ለመልበሱ እንጂ ከቅርብ ሴት ለመምሰሉ ጥርጥር አለው፡፡ እግሩን እየጎተተ ከመኪና በቀር እማራጭ እንደሌለው ያውቀዋል፡፡

ግራ ቀኝ እየተወሚመደ ሲራመድ ከቁስሉ ይልቅ ሀዘኑን መሸከም ያቃተው ይመስላል፡፡ ሀዘኑ ዝናብ እንደ አደረበት ምርጊት ከብዶታል፡፡

'ራቧን አጥፍታ ይሆን?' ሲል እሰበ ሜሮዳን በዓይነ ህሊናው እያየ፡፡ ማንኛውም የዴርቶጋዳ አባል በጠላት እጅ መውደቁን እንደተረዳ ራሱን ከማጥፋት ወደኋላ አይልም፡፡ በዴርቶጋዳ አባላት ጣት ላይ የሚጠለቀው ቀለበት ውስጡ በሲያናይድ መርዝ የተሞላ እንቡጥ ጌጥ አለው፡፡ የቁርጡ ቀን ሲደርስ ከእንቡጡ ጎን ያለውን ሌላ ትንሽ ጉጥ ጫን ማድረግ በቂ ነው፡፡ እንቡጥ ጌጡ በፍጥነት ይከፈትና ይዘጋል፡፡ በዚሁ ቅፅበት የሲያናይዱ መርዝ ሥራውን ያቀላጥፈዋል፡፡

'አታረገውም!' የጌራ ፊት የሀዘን ጭርንቁስ ለበሰ፡፡ በዓይኖቹ ውሃ ግጥም ብሎ እንደጉም ጋርዶ መንገዱን አሳሳይህ አለው፡፡ ሜሮዳ የቀለበቷን ጉጥ ስትጫን በዓይነ ህሊናው ተስላ ታየችው፡፡ ተስለምልማ ስትዝለፈለፍ ከዛም እነዛ ውብ ከንፈሮቿ ተከፍተው በፍንጭት ጥርሷ መሃል የሚወዳት ነፍሷ ወጥታ ስትሄድ ታየው፡፡ በአንድ እጁ አየሩን ቀዘፈ፡፡ ሜሮዳን ተዝለፍልፋ ስትወድቅ ለመደገፍ፡፡ ሱሉልታ ሊደርስ ጥቂት ሲቀረው ሙሉ ለሙሉ ነጋበት፡፡ ሱሉልታ ዓይኗን እሻሽታ ከእንቅልፏ ነቅታለች፡፡ ከአዲስ አበባ በስተሰሜን የምትገኘው ይህቺ የገጠር ከተማ ትንሽ ከመሆንዋ የተነሳ ወዘልውጥ ሰው ወዲያውኑ እንደሚለይ ያውቃል፡፡ አለባበሱም ሆነ አረማመዱ የሰዎችን ትኩረት እንደሚስብም ተረድቷል፡፡ ወደዚች ከተማ በዚህ ጊዜ መግባት ከፍተኛ አደጋን አቁርሮ እንደመግባት መሆኑን ተረዳ፡፡

ጌራ እርምጃውን ገታ፡፡ ጥቂት ካቅማማ በኋላ ወደ ምሥራቅ ተመለከተ፡፡ በደኖቹ ላይ እስከነሁን ጉም ይንጎማለላል፡፡ ቀረብ ወዳለው ደን አማተረ፡፡

# ፲፯

## አዲስ ዘመን + ኢትዮጵያ

በተራራው ከርስ ምድር ውስጥ ካሉ ልዩ ልዩ ክፍሎች ውስጥ ይህኛው ለየት ያለ ነው፡፡ ርዝመቱ 18 ሜትር ወርዱ 10 ሜትር የሆነው ይህ ክፍል፣ ድምጽ ወደ ውስጥም ወደ ውጭም እንዳያስተላልፍ ተደርጎ የተሠራ ነው፡፡ ግድግዳው ሰማያዊ፣ ጣራው ቀይ፣ ወለሉ ደግሞ ጥቁር፣ አብረቅራቂ ክፍል፡፡ ከወለሉ መሃል እጅግ ግዙፍ የሆነ ክብ ጠረጴዛ ይገኛል፡፡ መጠነዙሪያው የትየለሌ ነው፡፡ ቀዩ ክብ ጠረጴዛ ቀልጠ የፈነዳ እሳተገሞራ ይመስላል፡፡ መሀሉ ላይ ዮቶ ቅርፅ በብርማ ቀለም ተቀርፆበታል፡፡ በዙሪያው ባለግርማ ሞገስ ቀያይ ወንበሮች አሉ፡፡ ቁጥራቸው አይጨምርም፣አይቀንስም- አሥራ ሶስት ናቸው፡፡ በእያንዳንዱ ወንበር ላይም ከ፩ እስከ ፲፫ ቁጥሮች ተቀርፆባቸዋል፡፡ በወንበሮቹ ላይም ጥቁር ሙሉ ሱፍ ከቀይ ሸሚዝና ቀይ ከራቫት ጋር የለበሱ አሥራ ሶስት ሰዎች በአርምሞ ተቀምጠዋል፡፡አሥራ ሶስቱም ወንበሮች ዴርቶጋዳ፣ ራማቶሓራ እና ዧንቶዣራ ከተባሉት የድርጅቱ ህዋሳት መካከል በተውጣጡ ማዕከላዊ አለቆች የተያዙ ናቸው፡፡ አሥራ ሶስቱም እኩል ድምጽ እኩል ስልጣን አላቸው፡፡ ከአሥራ ሶስቱ ህዋሳት አንዱ ከጎደለ ምልአተ ጉባኤ አይካሄድም፡፡ ተራ ውይይትም ሆነ ስብሰባ ማድረግ የተከለከለ ነው፡፡ ቁጥር አንዱ የዴርቶጋዳ ማዕከል በዳጋ ደሴት ከርስ ምድር ውስጥ ከነደደ በኋላ በህይወት ከተረፉ ሁለት አባላት በቀር ሌሎቹ አዲስ ተመራጮች ናቸው፣ ከአዲሶቹ ተመራጮች ውስጥም ተራራው ከተከበበ ወዲህ ከተራራው ውጭ በቀሩት አባላት ምትክ የተመረጡ አዳዲስ አባላት አሉ፡፡

እንደተለመደው ሁላቸውም እኩል ብድግ ብለው በአሥራ ሶስተኛው ወንበር ላይ በተሰየሙት ፕ/ር በርናባስ በተባሉት ሽማግሌ እየተመሩ የድርጅቱን ቃለ-መሀላ ፈፅመው፣ ቃል-

ሲፋኑን ግብተው እኩል ተቀመጡ፡፡ ቃለ-መሃላውም ሆነ ቃለ-ሲፃኑ አልተሰወጠም፡፡ ያው የቀድሞው ነው፡፡ ምን-ምርናት ሰፍሯል፡፡ ከጥቂት የዕጥቃ ጊዜ በኋላ በ2ኛው ወንበር ላይ የተቀመጡት ሻ/ር ብርናባስ የጉባኤውን መጀመር በንግግር አበሰሩ፡፡ አጠር ካለው ንግግራቸው በኋላም የዕለቱን የመነጋገሪያ አጀንዳ አቀረቡ፡፡ የሰብሰባው አጀንዳ በየሁሉም ፊት ተቀምጦ በቀላሉ ማንበብ ይቻል ነበር፡፡ የመነጋገሪያው አጀንዳ የተራራውን መከበብና ከከበባው ለማምለጥ የሚነደፈውን ስሌት በተመለከተ ነበር፡፡ እንደባለፈው ስሜታዊ በሆነ መንገድ ሳይሆን በስክነት መልኩ ውይይቱ ቀጠለ፡፡ ከስብሰባው አዳራሽ ውጭ ያለው ከሁለት ሺህ ሰምንት መቶ በላይ የሆነው የተራራው ውስጥ ነዋሪ ሁሉ ድምፁን አጥፍቶና አድፍጦ የሚጠባበቀው የዚህን ስብሰባ ውጤት ብቻ ነው፡፡ ወጣም ወረደ ሁሉም ራሱን ለማዳን ብቻም ሳይሆን ድርጅቱ ውፍድፉ እንዳይጠፉ ባለው ልክ ፍላጎት አቋሙ ተፋልሞ ማምለጥ እና እንደገና ማቆጥቆጥ ነው፡፡

አብዛኛዎቹ የማዕከላዊ ኮሚቴው አባላትም ይህን የብዙሃኑን አቋም እንደሚያንፀባርቁ ተስፋ ተደርጓል፡፡ ከሁሉም በላይ ግን ሚራዥ የእንበሳውን ድርሻ እንደሚወስድ ታምኖበታል፡፡ እስካሁን እንፋለም በሚል ሀሳቡ ከመፅናቱም በተጨማሪ፣ ይህን ሀሳቡን ሲሰብክና ሲያግባባ ሰንብቷል፡፡ ሁለቱም በአንድ ልብ እንደሚያስቡ የሚነገርላቸው ሚራዥ እና ዣንጊዳ ተቃርኖ ያለው ሀሳብ ይዘው እንደማይቀርቡም ታምኗል፡፡

"ከቡራንና ከቡራት የኛ ህልውና የሚከስምበት ወይም በእንዳች ተአምር የሚቀጥልበት ወቅት ላይ መሆናችን ለማንም የሚደበቅ አይደለም፡፡" ሲል ነበር ሚራዥ ተራው ሲደርስ መናገር የጀመረው፡፡ "ብንጠፋ የምንጠፋ እኛ ብቻ አይደለንም፡፡ በመላው ዓለም ያሉ አባላቶቻችንና ዓላማችንን የሚደግፉ ኢትዮጵያን ህልም ጭምር ነፋስ እንደ መጣበት የሻማ ብርሃን ድርግም ይላል፡፡ የአባላቶቻችን ህልውናም አደጋ ላይ ይወድቃል፡፡ እስከ አሁኗ ደቂቃ ድረስም ህይወታቸውን አደጋ ላይ የጣልንባቸው አባላቶቻችን በመላው ዓለም መደበቂያ በማጣት እየተሹለከለኩ ይገኛሉ፡፡ ህልማችን ብቻ ሳይሆን እነዚህን ሰዎች የማዳን ኃላፊነትም አለብን፡፡ ጠላቶቻችን ወደዚህ ክርሰ ምድር ከገቡ በዓለም ዙሪያ ያሉ አባላቶቻችን ስምና አድራሻ በእጃቸው እንደሚገባ ማንም ሊጠራጠር

አይገባም፡፡ ስማቸውን ከኮምፒውተሮች ላይ ማጥፋት ከመዛግብት ላይ መሰረዝ በቂ አይደለም፡፡ በሰዎች አእምሮ ውስጥ ያለውን ዝርዝር መረጃ መሠረዝ አይቻልም፡፡ የጋለ ብረት አካሉ ውስጥ ሲሰነቀር የጋለ ብረት አጥንቱን በስቶ ሲያልፍ ማንም ቢሆን ቢለፈልፍ አይፈረድበትም፡፡ መቼም የጭንቅ ቅፅበት አያስተማምንም፡፡" አላንዳች እንቅስቃሴ በጥሞና የሚያዳምጡትን ሰዎች ፊት ቃኝት አድርጎ ንግግሩን ቀጠለ፡፡

"ቀድሞ እጅ አለመስጠትን የመሰለ ነገር የለም፡፡ አደጋን ቀድሞ መከላከልን ያህል ነገር የለም፡፡ እኛ ህይወታችንን ሙሉ የሰጠንለት ህልም ያለን ሰዎች ነን፡፡ ብንቆስልለት ቀርቶ ብንሞትለት የማንቆጭበት ህልም ያለን ሰዎች ነን፡፡ ይህን ስል ስለሕይወት ቁብ የሌለኝ ሰው እንዳይደለሁ ልታውቁልኝ ይገባል፡፡ በዚህ ተራራ ውስጥ ለዘመናት የደከምንባቸው የምርምር ውጤቶች እንዳሉን እውቃለሁ፡፡" ከመካከላቸው ማንም ባያስተውለውም ሁለት ሰዎች እርስ በእርስ ተያይተው እንደገና ሚራኸን በእንክሮ ያዳምጡት ጀመር፡፡

"ይህን ሁሉ ህልም በመና ጥለነው መሸሽ አለብን ብዬም አላምንም፡፡ ነገር ግን ከዚህ ሁሉ ማስቀደም ያለብን ነገር አለ፡፡ ይህን ሁሉ ጥበብ ያፈለቀው የሰው ልጅ ጭንቅላትስ? ህይወትስ? እም ስለ ህይወት ይገደኛል፡፡ ምርምሩን እንደገና ማካሄድ እንችል ይሆናል፡፡ ጭንቅላቶችን ግን እንደገና መፍጠር አንችልም፡፡ እኛ ሮቦቶች አይደለንም፡፡ ሰዎች ስለሆንን እንደገና አንገጣጠምም፡፡" ብሎ አመስግኖ ዝም አለ፡፡ 'ጌራ ቢኖር' ሲል ተመኘ፡፡ እሱ ቢኖር ኖሮ በእርግጠኝነት ሀሳቡን ይደግፈው እንደነበር እርግጠኛ ነው፡፡ ነገር ግን ጌራ ወደ ተራራው ሳይመለስ ተራራው በመከበቡ በእርሱ ፋንታ አክሎግ የሚባል ሰው በቁጥር ስምንት ወንበር ላይ ተቀምጧል፡፡

አክሎግ በሃምሳዎቹ መጨረሻ ላይ የሚገኝ ዝምተኛ ሰው ነው፡፡ ፊቱ ላይ የሚነበብ አንድም ስሜት አይገኝም፡፡ ሲስቅም ሆነ ሲያዝን ሲናገርም ሆነ ዝም ሲል ገፅታው ላይ የሚታይ አንዳች የሚገጥም አይመስለውም፡፡ የሚራኸ ኮከብ ከዚህ ሰውዬ ጋር ኮሚቴ አባል እንደሆነ ግራ ሲገባው ሰንብቷል፡፡ 'አብዛኛውን ጊዜ ማን ምን በምን እንዳገኘና ማን በማን የት እንዴት

እንደደረሰ አይታወቅም፡፡' ሲል አሰበ፡፡ አክሎግ በተራራው ውስጥ ታስሮ የሚገኘውን ታዲዎስ ኢያሱን ያናዝዝ የነበረ ሰው እንደነበር ብቻ ነው የሚያውቀው፡፡ ሚራዥ የአክሎግን ዝና ቢሰማም ግለ ታሪኩን ከመዝገብ ላይ አገላብጦ እንኳ አያውቅም፡፡ ከዚህ ስብሰባ ከወጣ በኋላ ግን ቀድሞ የሚያደርገው ተግባር የእርሱን ግለ ታሪክ ማገላበጥ እንደሚሆን ወስኗል፡፡ ባለፈው ሻጊዝን አንቂም ቢሆን እደራደርበታለሁ ሲል የተከራከረው ሰው ነበር፡፡ ዛሬ ምን ይናገር እንደሆን ይጠባበቀው ጀመር፡፡ መቼም ሻጊዝ እዚሁ ከመሃከላቸው ተቀምጦ ያንን አባባሉን ይደግመዋል የሚል እምነት የለውም፡፡ ሌላ አንድ ሰው ከተናገረ በኋላ የአክሎግ የመናገሪያ ተራ ደረሰ፡፡ ሚራዥ ዓይኖቹን አክሎግ ላይ ተከለ፡፡ አክሎግም ዓይኖቹን ሚራዥ ላይ አንቦገቦገ፡፡

"እይጥ ለመሞቻዋ የድመት አፍንጫ ..." ብሎ ሳይጨርስ ሳቅ አዳራሹን ሞላው፡፡ ከሚራዥና ከዣንጊዳ በቀር ያልሳቀ አልነበረም፡፡ አክሎግ ሳቁ ጋብ እስቲል ጠብቆ ሲቆይ ሌላ የሚናገር ይመስል ነበር፡፡ ነገር ግን ሌላ ቃል አልጨመረም፡፡ "ታሽታለች፡፡" ብሎ ቅድም የጀመረውን አባባል ጨርሶ ዝም አለ፡፡ አሁንም ሌላ ሳቅ ተከተለው፡፡ ሚራዥ በግኖ ዝም አለ፡፡ ተረኛው ተናጋሪ ዣንጊዳ ነበር፡፡

"ቀልድ..."ሲል ጀመረ- ዣንጊዳ መረር ባለ ቅላፄ፡፡ "ቀልድ፣ የህይወት ያንዳንድ ጊዜ ማጣፈጫ ቅመም፣ የህልውና ያልፏልፎ ማስጊጫ ቀለም እንጂ የቁምነገር ረመጥ የሚዳፈንበት አመድ አይደለም፡፡ ህይወታችንን ብቻም ሳይሆን ህልማችንን ለማትረፍ ያደፈጥን ፍጡሮች እንጂ ተረትና ምሳሌ ለመታደም አልተቀመጥንም፡፡ የተቀመጥንበት ቦታም ህልማችንን መደበቂያ ቦታ እንጂ የሮም እምፌ ቴያትር አይደለም፡፡"

"ይህ አጣብቂኝ ጊዜ የምንቀልድበት እንዳልሆነ እኔ በበኩሌ እገነዘባለሁ፡፡ ይህ ዓይነቱ ዋዛ ፈዛዛም ከዚህ ታላቅ ጉባኤ የሚጠበቅ አይመስለኝም፡፡ በእነዚህ አሥራ ሶስት ወንበሮች ላይ ስንቀመጥ፣ ከዚህ በፊት በነዚህ ወንበሮች ላይ ተቀምጠው የሰበሰቡትን ታላላቅ ሰዎች ማሰብ አለብን፡፡ ከዚህም በላይ የእነዚህን ወንባሮች ውሳኔ የሚጠባበቁ እያሌ ህይወቶች እንዳሉ ማሰብ አለብን፡፡ እንሩለም ወይም እንደራደር በሚለው ሀሳብ ዙሪያ ከየአቅጣጫው ብዙ ተብሏል፡፡ የእኔ ሀሳብ ከተባለው ሁሉ

የተለየ አይደለም፡፡ ነገር ግን ዕኑ አቋሜን ይህ የተከበረው ጉባኤ እንዲያውቅልኝ እፈልጋለሁ፡፡ እሱንም በአፅንኦት እናገራለሁ፡፡ ቃሌም ይኸው ነው፡፡ የምንደራደርበት ጊዜ ላይ አይደለንም፡፡

"ገገርው ስርዓት እንኳንስ በአንድ በህቡዕ በተደራጀ ቡድን ይቅርና በጥላው በሚደነግጥበት ሰዓት ላይ ነው ያለው፡፡ ጤፍ ተወደደ ብሎ ማማረር ሽብርተኛ የሚያስብልበት ጊዜ ላይ ነው ያለነው፡፡ ራበኝ ብሎ የዳቦ ጥያቄ ማንሳት ሽብርተኛ የሚያስበብልበት ጊዜ ላይ ነው ያለነው! ለተገቢው ሥራ ተገቢው ክፍያ ይከፈለኝ ብሎ መጠየቅ ሽብርተኛ የሚያስብልበት ጊዜ ላይ ነው ያለነው፡፡ ሥርዓቱ ካለፉት ሃያ ዓመታት በላይ ያልመለሳቸውን ጥያቄዎች ማንሳት ሽብርተኛ የሚያስብልበት ጊዜ ላይ ነው ያለነው፡፡ ቋንቋን መሠረት ያደረገው ፌደራላዊ ስርዓት ፀረ-አንድነትና ፀረ-እድገት ነው ብሎ መከራከር ሽብርተኛ የሚያስብልበት ጊዜ ላይ ነው ያለነው፡፡ የዘር ልዩነታችን ለፖለቲካ ፍጆታ አታውሉብን ብሎ መማጠን ሽብርተኛ የሚያስብልበት ጊዜ ላይ ነው ያለነው፡፡ ግብሩና ታክሱ ፍትሀዊ አይደለምና ይስተካከልልን ማለት ሽብርተኛ የሚያስብልበት ጊዜ ላይ ነው ያለነው፡፡ የመሬት ፖሊሲው ይከለስልን ያልነውን፣ ለዕለት የፖለቲካ ጥቅም አዋላችሁት እንጂ ለዘመናት ደም አፋሳሽነቱን አላስቆማችሁልንም ብሎ መጠየቅ በሽብርተኝነት የሚያስጠይቅበት ጊዜ ላይ ነው ያለነው፡፡ የዜጎች እኩልነት ለይስሙላ ሳይሆን ከልብ፣ የብሔረሰቦችም ጥያቄ ለዕለት ጉርስ ሳይሆን ለዘለዓለም... ይመለስልን ማለት በሽብርተኝነት የሚያስጠይቅበት ዘመን ላይ ነው ያለነው፡፡ እስካሁን የተናገርኩትን መናገርም በሽብርተኝነት እደሚያስጠይቅ አለመጠራጠር አይቻልም፡፡" ዣንጊዳ ይህን ብሎ አላበቃም፡፡ ሁሉንም በየተራ ቃኝቶ ቀጠለ፡፡

"እንደራደር የሚለው አካል 'እንደራደር' ሳይሆን ማለት ያለበት 'ወደ ቃሊቲ እንንደርደር' ነው፡፡ ዘመናዊ ጦር መማሪያ እስከ አፍንጫው ታጥቆ ተራራ ውስጥ የመሸገን ቡድን ይቅርና እጁን ኪሱ ከቶ መሃል አራት ኪሎ ላይ በሀገሩ ጉዳይ ሲብሰለሰልና ሲከራከር የሚውል እንኳ ምን እንደሚደረግ እናውቃለን፡፡ ምንድን ነው ምትሉት?....... ቃላት ለወረወረ ጥይት፣ ድንጋይ ለወነጨፈ ጀት በሚላክበት ሀገር ውስጥ መሆናችንን መርሳት የለብንም፡፡ በሚላክበት ሀገር ውስጥ

"እኔ ዣንጊዳ እንዲህ መሆኑን ባውቅ ኖሮ ይህን አልጨማለቅም ነበር፡፡ እኔ ብቻ ሳልሆን እዚህ ተራራ ያህል የሚገኙ ወንድሞቼ እና እህቶቼ የራሳቸውን ህይወት ውስጥ ሳይፈልጉ ቀርተው አልነበረም፡፡ አብዛኞዎቻችንም የመኖር ትኩስ ፒዛ ቅርጫት ውስጥ ከሚጣልበት የድሎት ዓለም የመጣነው የዳቦ ጥያቄ ኖሮብን አይደለም የመጣነው፡፡ ነገር ግን የምንበላው ከቁንጣን የዘለለ ጥቅም እንደሌለው በማወቃችንና በመገንዘባችን ነው እመጣጣችን፡፡ የወገኖቻችን ረሀብ፣ ጭቆና እና ግፍ አንቅልፍ ነስቶን ነው፡፡ እንደራደር የምትሉት ከማን ጋር እንደሆን አልገባኝም፡፡ የዘር ስካር አናታቸው ላይ ወጥቶ ከሚያንገዳግዳቸው የጦር አበጋዞች ጋር ነው? ለሃያ ዓመታት አንድ ጥያቄ መመለስ አቅቷቸው ለተጨማሪ አያሌ ዓመታት ለመግዛት ቀን ከሌት 'ፑሽ አፕ' ከሚሠሩት ጋር ነው? ... ዣንጊዳ ይህን እንደማይሞክረው ቃል እገባላችኋለሁ፡፡" ዣንጊዳ ይህን ብሎ ዝም ሲል ጥቂት ፀጥታ ሰፈነ፡፡ ሁሉም በክቡ ጠረጴዛ ላይ ዓይኑን ተክለ፡፡ ቀጣዩ ተናጋሪ ዣክ ዶናልድ ሲሞን ነው-ኘጊዝ፡፡

ኘጊዝ ምን ይናገር ይሆን? የሚለው የሁሉም ጥያቄ ነበር፡፡ ከሚራኝ ውትወታ በኋላ ሀሳቡን ሳይለውጥ እንዳልቀረና መጀመሪያም ይፈልግ የነበረው አሳማኝ ምክንያት እንጂ ሌላ እንዳልነበር ብዙዎች ገምተዋል፡፡

"ሁላችሁም ልብ የሚነካ ንግግር ተናግራችኋል፡፡" ሲል ነበር ንግግሩን የጀመረው፡፡ "የእኔ ንግግር እንደ እናንተ ልብ የሚነካ አይደለም፡፡ በመጀመሪያም የእኔ ፍላጎት ጥቂት ጥያቄዎች ይመለሱልኝ ዘንድ ነበር፡፡ እነዚህ ጥያቄዎች ሁልጊዜም ቢሆን የትኛውንም ውሳኔ ከመወሰናችን በፊት መመለስ ያለባቸው ናቸው፡፡ ለምን ጦርነቱን እንዋጋለን? እንዴት ጦርነቱን እንዋጋለን? መቼ ጦርነቱን እንዋጋለን? የት ጦርነቱን እንዋጋለን? በምን ጦርነቱን እንዋጋለን? እነማን ከማን ጋር ጦርነቱን ይፈለማሉ? የሚሉት ጥያቄዎች መመለስ ነበረባቸው፡፡ አሁንም ቢሆን እነዚህ ጥያቄዎች የሚመለከቷቸው ሰዎች ይኖራሉ፡፡ እኔ ሳይንቲስት እንጂ የጦርነት ልምድ ያለኝ ሰው አይደለሁም፡፡ ምናልባት እኔ መመለስ የምችለው ጥያቄ በምን ጦርነቱን እንፋለማን የሚለውን ይሆናል፡፡ ይህንንም ቢሆን ስሞኑን እየተዟዟርኩ ያሉንን መሣሪያዎች ተመልክቻለሁ፡ለከፋ

አይሰጡም፡፡ ሆኖም የእኛን የመሣሪያ ብቃት ብቻ ሳይሆን የተፃራሪ ኃይሎችን ብቃትም ማየት እስካልተቻለ ድረስ ይሄ ጥያቄ ተመልሷል ማለት አይቻልም፡፡ የተፃራሪ ወገን የመሣሪያና የሰው ኃይል ብቃት በውል መመዘን አለበት፡፡ የምንፋለመው በምሥራቅ አፍሪካ በወታደራዊ አቋምም ሆነ ብቃት ወደር የማይገኝለትን ሠራዊት ነው፡፡ ከሁለት መቶ ሰማንያ ሺህ በላይ ወታደር ካለው ሥርዓት ጋር መፋጠማችን ሊታወቅ ይገባል፡፡ ከዚህ ውስጥ ምን ያህል ወታደር እንደከበበንም ማወቅ ይጠበቅብናል፡፡ ከዚህም ባሻገር አካባቢውን በተመለከተ የተጠናው ጥናት መቅረብ አለበት፡፡ ሊሳም መረሳት የሌለበት ነገር አለ፡፡ ውጊያው አጭርና በጥበብ የተሞላ መሆን አለበት፡፡ ለአጭር ጊዜ፡፡ ቢያንስ በአንድ ሌሊት የሚጠናቀቅ ውጊያ፡፡ አላማችን የትጥቅ ትግል በማድረግ መንግሥት መገልበጥ እንዳልሆነ መረሳት የሌለበት ጉዳይ ነው፡፡ ከዚህ ጋር በተያያዘ አንድ ፍርሃት አለኝ፡፡

"የኑሮ ውድነቱ ቆሽቱን ያሳረረው ህዝብ የኛን የነፍስ አድን ውጊያ ተከትሎ አመፅ እንዳይቀሰቅስ እሰጋለሁ፡፡ ከዚህ ባሻገር ግን እንፋለም የሚለው አቋም የሚያወላዳ አይደለም፡፡ ወደን ሳይሆን በሁኔታው ተገደን እንፋለማለን፡፡ 'ህልም ተፈርቶ ሳይተኛ አይታደርም፡፡' እንዲሉ ይህን ውጊያ አድርገን መንገድ የማስከፈትና ህልማችንን የማስቀጠል ብሎም ሰዎቻችን የማዳን ግዴታ አለብን፡፡" ሻጊዝ ይህን ብሎ ሚራዥን በጨረፍታ ተመለከተው፡፡ ፊቱ ተፈቷል፡፡

ከዚህ በመቀጠል የመናገር ተራ የደረሰው አያና ተፈሪ የተባለውና በቅርቡ ለመመረጥ የበቃው አባል ነበር፡፡ እጅግ ወግ አዋቂ ቢሆንም የአሁኗ ንግግሩ ግን ቅልብጭ ያለች ነበረች፡፡

"ይህን ጦርነት መጀመር ሀገሪቷን ወዳልተጠበቀ የእርስ በእርስ ጦርነት መክተት ነው፡፡" ሲል ተቃወመ፡፡

ከብዙ ክርክር በኋላ ጉባኤው እንፋለም የሚሉ ሰዎች ድምፅ እንዲሰጡ ተደረገ፡፡ አሥር ድምፆች እንፋለም የሚለውን ሀሳብ ሲደግፉ ሁለት ድምፆች እንደራደር የሚለውን ደግፈው አንድ ድምፅ ደግሞ ድምፀ ተአቅቦ አደረገ፡፡ ሁለቱ እንደራደር የሚሉት ድምፆች የተቆጠሩት ከአክሊሉግና ከአያና ተፈሪ ነበር፡፡

ሆኖም በድምጽ ብልጫ እንዲለም የሚለው ጸደቀ፡፡ ጉባኤውም ለፋልጊያው ጉዳይ ለመነጋገር ቀጠሮ ተይዞ ተዘጋ፡፡

ስብሰባው ሲወጣ ሚራዥ መንፈሱ ታውኮ ነበር፡፡ የእክሎግና የአየና ሁኔታ አላማረውም፡፡ ለከፋም ለደጉም በውጊያው ጉዳይ ላይ የሚቀርቡ ጥናቶችን ባይከታተሉ ምኞቱ ነበር፡፡ ይህንን ግን ለማንም ለመግለጽ አልደፈረም፡፡ ከስብሰባው አዳራሽ እንደወጡ ሻንጊዳን በዚህ ጉዳይ ላይ ለማነጋገር ወደ ቢሮው ይዞት ሄደ፡፡

# ፲፰

## ፍሎሬንስ

የአባቱን ማስወታሻ ማገላበጡን ተያይዞታል - ኪራኮስ፡፡ አባቱ እጅግ ውስብስብ ስለሆኑት ምስጢራዊ ማህበረሰቦች የፃፉት ይህ ማስታወሻ መንደርደሪያው አስገርሞት ሊያበቃ አልቻለም፡፡የምስጢራዊ ማህበረሰቦች የወል ባህርይ እና አጠቃላይ ገፅታ፣ ታሪካቸው፣ አነሳሳቸው፣ አወዳደቃቸው እና ተፅዕኖአቸው በሽማግሌው ማስታወሻ ውስጥ በሰፊው ተብራርቷል፡፡ ኪራኮስ ይህንን ዳጎስ ያለ ማስታወሻ ከመጀመሪያው ገፅ ጀምሮ በመመርመር ላይ ነው፡፡

ስምባገንናዊ ስርዓት በህቡዕ እንጂ በገሀድ መቃወምንም ሆነ መደራጀትን የሚፈቅድ ባለመሆኑ በህቡዕ የሚገኘው ቡድን ስያሴ ይሆናል፡፡ የስምባገንናዊ ሥርዓት ባለስልጣናትም በህቡዕ የሚንቀሳቀሱትን ቡድኖች በየስርቻው ለማነፍነፍም ሆነ ስልጣናቸውን ከስጋት ለመከላከል ስያሴ የህቡዕና የገሀድ ኃይላትን ከማቋቋም አይቦዝኑም፡፡
ሲል የሽማግሌው ማስታወሻ ይጀምራል፡፡

ባለስልጣናቱም ህቡዕ የገቡባቸውን ቡድኖች ለንገት ፈጥራቂ፣ ለነፍናፊ ኃይል ለማቋቋም ሲሉ የሀገርን ሀብት ለዚሁ ጉዳይ ወጪ መሸፈኛ ያውሉታል፡፡ እንዲህ አይነቱ የስደጥና የድመት ተግባር ከፍተኛ ገንዘብን፣ ጉልበትንና የሰው ኃይልን ስለሚጠይቅ የባለስልጣናቱ ሀሳብ፣ እውቀትና ሀብት ሁሉ ለዚህ ተግባር ይውላል፡፡ ድመት ባለበት ሀገር ዓይጦች ያለጉድጓድ መኖር አይችሉም፡፡ የዓይጦቹ ጉድጓድም ጠልቆ የተቆፈረ ብቻም ሳይሆን የውስጥ ለውስጡ ጥምዝና ጉራንጉር ለድመቶች እንዳይመች ተደርጐ መሠራት አለበት፡፡ የዓይጦቹ ገደልም ድመቶችን እንዳያስገባ ተደርጐ መቆፈር አለበት፡፡የድመቶቹ ጥፍሮችም ከመጧጠጥ አይቦዝኑም፣ ሁልጊዜም የሾሉ ናቸው፡፡ዓይኖቻቸውም ከአይጦቹ ገደል ላይ አይነሱም፡፡

እየሚዘን የፈጸሁት እንዲህ ዓይነቶቹን የምስጢር ድርጅቶች በማጥናት ነው። ኢትዮጵያ ውስጥ የህቡዕ ቡድኖች ለበጣ የአጭር ጊዜ በመሆኑ፣ ዓላማቸው ሊያበቃ ይበታተናሉ። ለመፈንቀለ መንግስት፣ ለዝርፊያ፣ ለማሰደን ምንነቱ ወዘተረፈ የሚቋቋሙት ዓይነት ቡድኖች ከነዚህ የሚካተቱ ናቸው። ከነዚህ ሳት ያሉት የረጅም ጊዜ እቅድ አውጥተው በዘላቂነትም ለመኖር የሚንቀሳቀሱት ናቸው። የእኔ ትኩረት ሆነው የኖሩትም እነዚህ ናቸው። ኢትዮጵያ ውስጥ የተቋቋሙት ህቡዕ ድርጅቶች ከሌሎች ዓለምአቀፋዊ የምስጢር ድርጅቶች የወረሱት አደረጃጀት የወረሱት ጠባያም ሆነ መዋቅር መኖሩ ለሌ የሚባል አይደለም።

በኢትዮጵያ የተቋቋሙትን ህቡዕ ድርጅቶች ሁለመና ከመጠቃቀሉ በፊት ዓለም አቀፋዊ የሆኑትን ምስጢራዊ ማህበረሰቦች ታሪክ፣ መጠቃቀሉ ተገቢ ነው። ምክንያቱም የዘመናችን ምስጢራዊ ማህበረሰቦች የነዚህ ቀደምት የሆኑት ምስጢራዊ ማህበረሰቦች ውጤት ናቸውና ነው።[፻]

ኪራኮስ ትንፋሹን ያዘ፡፡ ከሽማግሌው ማስታወሻ አንዲት ሀረፍተ ነገር እንኳ እንዳታመልጠው በመጠንቀቅ ይመረምረው ገባ፡፡ ሽማግሌው ዓለማቀፍ ምስጢራዊ ማህበረሰቦችን መዘርዘሩን ተያይዘውታል፡፡

## ቴምፕላሮች

እ.ኤ.አ. 1118 ዓ.ም.። ዘጠኝ ወታደሮች ወደ ኢየሩሳሌም ይመጣሉ- ከፈረንሳይ ተነስተው። ወታደሮቹ ወደ ኢየሩሳሌሙ የወቅቱ ንጉሥ ወደነበረው ወደ ባልድዊን ሁለተኛ (ዳግማዊ ባልድዊን)ይቀርባሉ። ለንጉሡም ለዓማቸውን ያስረዳሉ። ለዓማቸን ያሉት እለማ፣ ወደ ቅድስቲቷ ኢየሩሳሌም ከተማ የሚመጡትን መንፈሳዊ ተጓዦች ከቀማኞችና ከነፍሰ ገዳዮች መጠበቅ ነበር። መኖሪያቸውን ፈርሶ በነበረው የንጉሱ ሰለሞን ቤተ መቅደስ አቅራቢያ በማድረግ የኢየሩሳሌምን መንገድ መጠበቅ። ንጉሡ ጥያቄያቸውን ተቀበለ። «የሰለሞን ቤተ መቅደስ ጠባቂዎች» የሚል መጠሪያም አገኙ- «ቴምፕላሮች»።

ቴምፕላሮች በእርግጥ የኢየሩሳሌምን መንገድ መጠበቅ ነበር አላማቸው? አልነበረም። ከመንገድ ጠባቂነት ወደ ኢየሩሳሌም ጠበቃነት ለመሸጋገር ጊዜ አልፈጀባቸውም። በሰለሞን ቤተ መቅደስ ፍርስራሾች ውስጥ የተቀበረትን ቅርሶች ማፈላለግ ዋነኛ ሥራቸው ሆነ። የሰለሞን የወርቅ ንድፍቶች፣ የወርቅ

ለጥዎች፣ ዓለማቀፍ ታላላቅ ቅርሶችና የቃል ኪዳኑ ታቦት የዋና ዋና ስላማወቻቸው ማጠንጠኛ ሆኑ::

ቴምኘላርች ዘጠኝ ነበሩ:: ከዘጠኙ ሴላ የመጀመሪያው ስባላቸው ስንድ የፈረንሳይ ካውንት ነበር- ካውንት ቻምፓኝ:: የናጠጠ ባለፀጋ ነበር:: ከዚህ በኋላ በመላው ስውሮፓ ዝናቸው ስንደ ወረርሽኝ ከወዲያ ወዲህ ተዳረሰ:: ብዙ ስባለትን ከማፍራታቸውም ሴላ ስያሴ ካቴድራሎቻቸውን ስነፁ:: መንገድ ስመጠበቅ ስና የሃይማኖት ተጓዦችን ከዘራፊዎች ስመታደግ ብቅ ያሉት ወታደሮች በፍጥነት ወደ ባለ ሀብትነት ተሰወጡ:: ስንደነሱ ሀብት ያለው ድርጅት በመላው ስውሮጳ ቢታሰስ ታጣ:: ባጠራቀሙት የደለበ ሀብት በመላው ስውሮጳ ካቴድራሎቻቸውን ከማነፅ ባሻገር ብዙ ስባላትንም ሸመቱበት:: የነሱ ስባል መባል በራሱ ስንደ ከብርና መኩራሪያ ይቆጠር ጀመር:: ስንኳዋንስ በነሱ ውስጥ ስልጣን ማግኘት ተራ ስባል መሆን በራሱ ጥቅሙ የትየለሌ ሆነ::

በቴምኘላርች ሥልጣን የላይኛው እርከን ላይ ቁንጮ ሆኖ የሚቀመጠው "ግራንድ ማስተር" ተብሎ ይጠራል:: በ1118 ዓ.ም. ሥልጣን የያዘው የመጀመሪያው ስቢይ ስሰቃ የፓየንሱ ሁስ ነበር:: በየስንዳንዱ ሀገር የቴምኘላርች ስሰቃ ሲኖር ተጠሪነቱም ስማዕከላዊው ስቢይ ስሰቃ ነው:: የመጨረሻውና 23ኛው የቴምኘላርች ስቢይ ስሰቃ የሞዩ ጃኩየስ ሲሆን፣ በ1219 ዓ.ም. ስንደሞተ ይነገራል::

ስነሳላቸው በሰላም ስንደነበረው ስጠፋፋቸው በሰላም ስልነበረም:: የኋላ ኋላ ዋናው ምስጢራቸው ያፈተልክ ጀመር:: በቴምኘላርች ላይ ከፍተኛ የህዝብ ተቃውሞ (በዓለም ዙሪያ) የተቀሰቀሰው በጣፃት መልክ ስይጣንን ማምለክ በመጀመራቸው ነው:: ዝነኛው ጣፃታቸው ባፎሜት ይባላል:: ምስሉም... የሚከተሰው...ነው::



The Sabbatic Goat

ባፎሜት በቴምፕላሮች "The power of directed will" በመባል ይቀላመጣል:: ጭንቅላቱ የፍየል ሆኖ ግንባሩ ላይ አምስት ጎን ያለው ኮኮብ አለበት:: ሰዮት ያለው የስሙ ትርጉምም "የመረዳት አባት (Father of understanding)" ነው:: ቀንዱ፣ አገጩ፣ ጭንቅላቱ፣ ፊቱና ቀሪ የጣዖት ክፍሎች እያንዳንዳቸው መላምታዊ ትርጓሜ አላቸው::

ራሱ ለብቻው ሲወሰድ የአልኬሚስቶችን ምልክት ይመስላል:: ጭንቅላቱን የመጀመሪያው አቢይ አለቃ የፓየኑሱ ሁስ ነው የሚሉም አሉ::

እኛ የሰለሞን ቤተ መቅደስ ጠባቂዎች ነን፣ እኛ የክርስቶስ ወታደሮች ነን፣ እኛ የኢየሩሳሌም መንገድ ጠባቂዎች ነን እያሉ ሲያምታቱ የኖሩት ቴምፕላሮች ይህን የመሰለ ጣዖት በማምለክ ከክርስትና ውጭ የነበረውን ማህበረሰብ በመቅረብ ለመበዝበዝ ሞክረዋል:: ክርስትናን በሰይፍ እናስፋፋለን ብለውም መስቀል ከሰላጢን ጨብጠዋል:: ነገር ግን በጦርነት ውስጥ ራሳቸውን ደብቀው ሀብት ለመመዝበርና ለመዝረፍ እንደመቻቸው እንጂ ለሌላ አልነበረም::

በመካከለኛው ዘመን ሃይማኖት ከፖለቲካ ሥልጣን እንደሚበልጥ በማወቃቸው መደበቅ የፈለጉት በሃይማኖት ውስጥ ነበር::ቴምፕላሮች አላማቸው ሀብት እንጂ፣

ሃይማኖት እንደፀነበር የሚያስረዳው፣ ጠንካራና ውስብስብ የሆነ የባንኩ አሠራርን መዘርጋታቸው ምስክር በመሆኑ ነው:: ሀብትን በማጋበስም ምዕመናን አስቀድመው ለመጨበጥ ይጣጣሩ ነበር::

ለዚህም ነው በሊዮሪላሊም በስደት ይኖር የነበረውን ላሊበላን ወደ ኢትዮጵያ በመላክ ሥልጣን እንዲይዝ ያደረጉት:: ይህ የሆነው በ1185ዓ.ም ነው:: ላሊ ወደህም ኢትዮጵያ ውስጥ የተለያዩ የሚያስመስሉ ጥንብሱችን እያጠሰቁ በመገንባት ጥንታዊ ቅርሶችንና እውቀቶችን ዘርፈዋል::

በቀላሉ ይህን ለማስረዳት ጀምስ ብሩስን መጥቀስ ይቻላል::ጀምስ ብሩስ ጥንታዊውን ክብረ ነገሥት መጽሐፍና መጽሐፈ ሄኖክን ሰርቆ ሄዷል:: እነዚህ መጻሕፍት ሰሰርቅቱ ማስረጃ ይሁኑ እንጂ ይህ የቴምፕላሮች ቅጥረኛ ሆኖ የተላኩ ሰው ቢሉች ለያቢ እውቀቶችን ይዞ ላለመሄዱ ማስረጃ የለም::

እውቁ አሳሽና ባህረኛ ቫስኮ ደጋማም በ1493ዓ.ም. ወደ ኢትዮጵያ ገብቶ ያጠናውን አጥንቷል:: የቫስኮ ደጋማ ልጅ ክርስቶፎር ደጋማ ከዘመናት በኋላ 450 የፖርቹጋል ወታደሮችን እየመራ የጦሩ አዛዥ ሆኖ በ1541ዓ.ም. ወደ ኢትዮጵያ ገብቶ ነበር:: ይህ ክርስቶፎር መሪነት የፖርቹጋል ወታደር ከግራኝ አህመድ ወረራ "ኢትዮጵያን ለመታደግ" ይምጣ ወይም የተቀበረውን እውቀት ለመመንደግ ይምጣ አይታወቅም:: ነገር ግን ያባቱን አመጣጥ አይቶን ከዘመናት በኋላ የልጁን አመጣጥ ሥናይ እውቀትን ለመዝረፍ እንደነበር መገመት አያዳግትም:: ጸር የመጣው አባቱ ቫስኮ ደጋማ የቀም አስረኛ ተደርጉ እንደነበረ የታሪክ መዛግብት ያስረዳሉ:: በኋላ የመጣው ልጁ ክርስቶፎር ደጋማ ግን በግራኝ አህመድ ሰይፍ ተቀልቷል:: ምናልባት ወታደሮችን ምክንያትን ተጠቅሞ በማስከተል የመጣውም አባቱ የጠቀሙትን ምስጢር ቢችል በሰላም አልያም በጦርነት ለመንጠቅ መሆኑን መጠራጠር ያስረልጋል:: ይህ የሚታወቀው የአህመድ ግራኝ ሰይፍ ቁርስ ባያደርገው ነበር::

ወደ ተነሳንበት ፍሬ ነገር ስንመለስ . . . የቴምፕላሮች ሲሪ ዓለምን እየጨመደደ ሲመጣ እንደተኩላ በመላው ዓለም እየተሽሎከሎኩ ያካበቱትን ሀብት የበበሉት የበግ ለምድ ሲሸፍነው ላይችል ሲቀር መጨረሻቸው የቀረበ መሰሉ ነበር::

እ.ኤ.አ. በ1307ዓ.ም. በፈረንሳይ ንጉሥ ፍሊፕ 4ኛ አይቀጡ ቅጣት ተቀጡ:: በጣዖት መለዋዕት ከማቅረብ ጀምሮ ፀያፍ አማማምንና ቅንዝርናን፣ ገብረ ሰዶምንና የሞራል ዝቅጠትን በማሰማመድ ፀ-ገብረገብነትን አስፋፍተዋል በሚል

በቀረበላቸው ክስ እየተሰቀሉ ይታሰሩ ጀመር። በፈረንሳይ 15000 የሚሆኑ ቴምፕላሮች በአንዲት ጀምበር ተሰቅለዋል።

## ፍሪሜሶን



ቴምፕላሮችን ከነአካቴው መደምሰስ አልተቻለም። በዓለም ዙሪያ እንደ እንክርዳድ ቢሰቀሉም፣ ስንዴው ሲጠራ አልቻለም። እስስት መልኳን እንደምትለውጥ ቴምፕላሮችም ወዲያውኑ መልካቸውን ቀየሩ! የወንድማማቾች ማህበር (ፍሪሜሶን) በሚል ያደራጁት አዲስ ምስጢራዊ ቡድን ተሳዳጅ ቴምፕላሮችን እየተቀበለ ይደብቅ ጀመር።

ከዚህ በላይ የተቀመጠው ምልክት የፍሪሜሶኖች ነው። ኮምፓሱና ቲ-ስኩየሩ ወደ ፍፅምና የሚደረገውን እንቅስቃሴ (movement towards perfection) እና በቁሳዊውና በመንፈሳዊው አካል መካከል ያለውን ሚዛን (a balance between the spiritual and physical) ይወክላሉ። ኮምፓሱ ክብን ለመስራት ያገለግላልና መንፈሳዊ አካልን ይወክላል። ማስመሪያውም ቁሳዊውን አካል ይወክላል። ይህን አይነት ምልክት የጥንት ግብፃውያንም ይጠቀሙ እንደነበር ተመራማሪዎች ያስረዳሉ። ምልክቱን ይህን ያረገው ይህ ህቡዕ ድርጅት ተባራሪ ቴምፕላሮችን እየሰቀመ መደበቅን ገፋበት።

የቴምፕላሮች ለቢይ ለሰቃ የነበረውን ሚኒች ደግሞ መበቀላቸውን ማብሠሪ ነበር:: ፍሪሜሰኖች ኢሉሚናቲ የሚል ቢላ ግዙፍ ምስጢራዊ ማህበረሰብ በማቋቋም ዓለምን ወደፈለጉበት ደነዱ ዘንድ ከዚህ በኋላ ማንም ለሳለቁማቸውም::

# ኢሉሚናቲ



ብዙ ሰዎች ስለ ኢሉሚናቲዎች እውቀት የላቸውም:: ቢኖራቸውም እውቀታቸው ብዥታ ያጠላበት፣ ለደጨበጤ ነው::

ኢሉሚናቲ የሚለው ስያሜ ከላቲን ቃል የተወረሰ ሲሆን ላቲናዊ ትርጉሙም "ኢንላይትድ" (በእብርሆት የተቃኘ) ማለት ነው:: ይህ ቃል ለብዙ ምስጢራዊ ቡድኖች መጠሪያ የሆነ ስያሜ ነው:: ሆኖም የኢላይንትመንት ዘመን ምስጢራዊ ማህበረሰብን የሚገልጽ ነው:: በዘመናዊ ትርጉሙ "ማስተር ማይንድ" (የረቀቀ አእምሮ) ያላቸው ምስጢራዊ ማህበረሰቦች በአጠቃላይ የዓለምን ሁኔታ በተለያዩ ሀገራት መንግሥታትና ግዙፍ በሆኑ ዓለማቀፍ ድርጅቶች ሪጅም እጃቸውን በማስገባት የአዲሱን ዓለም ትዕዛዝ ለመገንባት ያሰለፉት የሚሰሩትን ህቡዕ ቡድኖች የሚገልፅ ነው:: የኢሉሚናቲ እንቅስቃሴ መቼ ተመሠረተ?

የኢሉሚናቲ እንቅስቃሴ እ.ኢ.አ1776ዓ.ም፣ ኢንጉዕስታድ በተባለና የላይኛው የባቫሪያ ግዛት በሆነ፣ የጀርመን ሀገር፣ በአምስት ግለሰቦች ተመሠረተ- በኢየሱሳዊያን:: ዋናው መሪም አደም ዊሻፕ የተባለ ግለሰብ ነው፤ በኢንጉዕስታድ ዩኒቨርሲቲ ፕሮፌሰር የነበረ:: እንቅስቃሴውም የኢንላይትመንት (የእብርሆት) ቅጥያ ሆኖ የነፃ አሳቢዎች (Free thinkers) ማህበር ይምሰል እንጂ፣ ፍሪሜሰን የተባለው እንቅስቃሴ ዐንቃጭ ነበር:: ስማቸውን እንደማርሽ በመቀያየር ወደር ያዐተገኘላቸው ቴምፕላሮች የዐጅ ዐጅ! ብዙ የኢሉሚናቲ ሳጋዎች የተመዘዙትም ቀድሞ ከነበረው "ሚሰናዊ" ጎጆ ነበር::

የኢሉሚናቲ አባላት በከፍተኛ ደረጃ ምስጢር ጠባቂዎችና ለበላዮቻቸው ታዛዥ የመሆን ግዴታ ነበረባቸው:: ሁሉም የኢሉሚናቲ አባላት ብዙ ዲግሪ ያላቸውና የተማሩ መሆን ይጠበቅባቸዋል:: በመሠረቱም አደም ዊሻፕ የትዕዛዙን ማጠንጠኛ ፍፁማዊነት ብሉት ነበር:: በዚህም ምክንያት ብዙ ተፅእኖ ፈጣሪ

ምሁራንና ፖለቲከኞች ፍሉማን ለመባል የኢሉሚናቲ አባል አድርገው ራሳቸውን ቆጠሩ:: ዣዬር ቮን ዋከን የመሳሰሉ (በኢሉሚናቲ ምሲጢራዊ ማህበረሰብ ውስጥ ሁለተኛው ሰው) የመሳሰሉ ዲፕሎማቶች፣ አባሉ ቹ ለመሆን በቁ:: በብዙ ሀገራት ቅርንጫፉን በማስፋት አህጉራቱን እንደ ሰርዶ ዉምድድ ያዛት:: በ10 አመታት ውስጥ ብቻ ከ2,000 በላይ አባላትን አበጀ:: ውሰጡ በአሪት የተሰወሰው "ክንፉ ማሰብ" የሚለው ጣፋጭ ዘሳብ እና ምዕፍጋንግንና ጎተን የመሳሰሉ ፀሀፍትን ሳይቀር ሰመሳብ በቃ::

እ.ኤ.አ. በ1777 ካርል ቲዎዶር የተባለ ሰው የባቫሪያ ገዢ ሲሆን ኢሉሚናቲዎች ላይ ጸጤዐም ጀመር::ገዢው የኢሳይንቲመንት እንቅስቃሴ ተጻራሪ ነበር:: የኢሉሚናቲ ሞት እየተቃረበ ሲመጣ አዳም ዊሻፕ ሲያመልጥ፣ የተገኙት ዶሴዎች በመንግሥት እየታተሙ ምስጢራቸው ተጋለጠ:: የምክትሉ የቮን ዋሌ ቤትም ተበርብሮ፣ የኢሉሚናት አባላት ሰሁፎች ተያዙ::

እ.ኢ.አ. በ1797 እና 1798 መካከል የታተሙት መጻሕፍት የኢሉሚናቲን መኖርና እንዲያውም ከፈረንሳይ አብዮት ጀርባ እንደነበር በማጋለጣቸው አስማቀፋዊ ውዥንብርንና አለመረጋጋትን ፈጠሩ:: ብዙ ፀሀፍትም የኢሉሚናቲ እንቅስቃሴ እስከ አሁን እንዳለ ይገልፃሉ:: አያሌ መላምቶች የዓለማችን እያንዳንዷ እንቅስቃሴ ሁሉ በኢሉሚናቲ ቁጥጥር ሥር እንደሆነች ይገልፃሉ:: ታዋቂ ገለሰቦችና መሪዎች የዚህ ምስጢራዊ ማህበረሰብ አባላት እንደሆኑ የሚከራከሩ አሉ:: ከነዚህ መሪዎች ዉስጥ ዋነኞቹ የአሜሪካ መሪዎች እንደሆኑም አጥብቀው ያስረግጣሉ::

በኢትዮጵያም የቀድሞው ንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለ ስላሴ የዚሁ ምስጢራዊ ማህበረሰብ አባል እንደነበሩ የሚከራከሩ አልጠፉም:: በሬት የፈረንሳይ፣ በኋላም የእንግሊዙ የኢሉሚናቲ ህዋስ በንጉሱ ላይ ተፅዕኖ አድርገባቸዋልም መዐምራቻቸዋልም ብሉ ሰመጠርጠር የሚያስችል ሁኔታ አለ:: ቴምፕላሮች ኢየሩሳሲም ይኖር የነበረውን ሳሲበሳን አምጥተው እንዳነገሱትም አጤ ቴዎድሮስ መቅደላ ላይ ከተሰው በኋላ ልዑል አለማየሁ ቴድሮስን በመውሰድ በኢሉሚናቲ ትምህርትና ምኞት አጥምቀው ኢትዮጵያ ላይ ለማንገሥ ፍላጎታቸው ነበር:: ከፍተኛ ትምህርት ይከታተል እንደነበርም መዛግብት ያስረዳሉ:: ሆኖም ልዑል አለማየሁ ያለ እድሜው የተሸከመውን ጭንቀት መሸከም ስላልቻለ በማረፉ ይህ ሴራቸው አልተሳካላቸውም::

በጣልያን ወረራ ጊዜ ወደ እንግሊዝ የተሰደዱት ኃ/ስላሴ ሲመለሱ፣ ዊንጌት የተባለ ኮ/ል በሚመራው ጦር ታጅበው ነበር በምስራቅ በጅቡቲ ወጥተው፣ በምዕራብ በሱዳን የተመለሱት:: ዊንጌት መራሹን ጦር ከጥንቱ ክርስቲያኖች ጀጋማ መራሹ ጦር ጋር ማመሳሰል ይቻላል:: ድጋፍ ሰጪ መሰሉ የሚመነደገው

የሰመናት ምኞት ብቻ አልነበረም የነበረው፤ ኢትዮጵያ በኢሉሚናቲዎች እንድትመራ የማመቻቸት ሥራውን ሠርቶ ለመመለስ ነበር። ለዚህ ደግሞ የመጡትን እንግሊዞችን ለመሰናበት ወደ ሀገራቸው መሸኘት ቀላል አልሆነም። ለስኬታቸው ቆይተው ከጣልያኖች በላይ በኢትዮጵያውያን ስነልቦና ላይ የሚፈልጉትን ፈጽመው ነበር የተመለሱት። ሀገር ወዳድ አርበኞች እንግሊዞችን ተቃውመው ሀገራቸውን ለማልማት እንደሞከሩ ያለበዘበዙት ትከሻቸው ለሹመት፣ ለገዢ ሲመጣ ክ/ብ የነበረው ዊንጌትም የጀነራል ማዕረግ ተቀብሎ ከዚህ በኋላ በስሙም ትምህርት ቤት ተሰየመለት። አብዛኛዎቹ የሀገሪትዋ ተሰሚ ፈላጊዎች ያሉኖችን መሪዎች ጨምሮ የወጡት ከዚሁ ትምህርት ቤት መሆኑን ልብ ይሏል። ያሉናቹ መሪዎችም ከጫካ ጀምሮ የእንግሊዞች እንክብካቤ አልተለያቸውም። ጠቅላይ ሚኒስትሩ በ1997 ዓ.ም.፣ ቶኒ ብሊየር ለተባለ የእንግሊዝ የወቅቱ መሪ፣ 'እኔ የጀነራል ዊንጌት ተማሪ ነኝ፤ አስተማሪዎቼም እንግሊዛውያን ነበሩ። እንደማንኛውም አፍሪካዊ የነጮች ጥላቻ የለብኝም፤ ከፍተኛ የሆነ የእንግሊዞች ተፅዕኖ በአመለካከቴም በቋንቋዬም አለብኝ' ሲሉ መናገራቸውን ጥቂት ልብ ባዮች ብቻ የተገነዘቡት ነው። በትግሉ ፍጻሜ፣ ሪብ እንግሊዛዊ በሆኑት በነባሩ ታጋይና አራጊ ፈጣሪ ሰውዬ እንግሊዞች ሙቢ መርገጣቸው ለዚህ ነው። ለማሳያት ከድል በፊት ዋና ቢሮአቸው እንግሊዝ ሀገር እንደነበር ማን ይዘነጋል? ሲላው ቀርቶ በደርግና በኢህአዴግ የተደረገው የእንግሊዙ ጆርጅ እንኳ ከዚህ ተለይቶ የሚታይ አይደለም። የኢሉሚናቲዎች ምልክቶችና አስተሳሰቦች አሁንም በሀገራችን መፈንጨታቸው ይህን ያረጋግጣል።

ለምሳሌ ያህል ባለ አምስት ጎኑን ኮከብ እንጥቀስ- ፔንታግራምን። ፔንታግራም የኢሉሚናቲዎች ምልክት መሆኑን ማንም የሚስተው አይደለም። በኢትዮጵያ ሰንደቅ አላማ ላይ የተቀመጠውን ባለ አምስት ጎን ኮከብ ብዙዎች ይቃወሙታል። አንዳንድ ቀልደኞች አንባሻ ነው ሲሉም ተሳልቀዋል። ይሁን እንጂ ምልክት (symbol) የጋራ ስሜትና አመለካከት መገለጫ ነውና እንዲህ ተቀልዶ የሚታለፍ ጉዳይ መሆን ባልነበረበት። በህገ መንግሥት የተሰጠው ትርጉምም አሻሚ ነው። "ብሔሮች፣ ብሔረሰቦች፣ ህዝቦች እና ሃይማኖቶች በእኩልነትና በአንድነት ለመኖር ያላቸውን ተስፋ የሚያንፀባርቅ' የሚል ትርጉም ቢጤ ተለጥፎበታል። የአርማ ውድድሩን ያሸነፈው፣ አፈሩ ይቅለለውና፣ መስፍን ሃ/ማርያም የተባለ ሰዓሊ እንደነበር የታወቀ ነው። እርሱ የሳለው ኮከብ መስመሮ አንዱ በአንዱ ላይ የማይተሳሰፍ ቢሆንም፣ በኋላ ግን መስመሩ አንዱ በአንዱ ላይ የሚተሳሰፍ ድፍን ኮከብ፣ አረንጓዴ ቢጫ ቀዩ ላይ ሲታይ ማንም ምንም አላለም። ይህም ሀገሪቷ ውስጥ የሚወጡ ህጎች ዜጎችን በማስፈራራት ወይም በመዝበዝ እንጂ የህግን ስነ ሥርዓት በማስከበር እንዳልሆነ በገሀድ የሚያሳይ ነው። ባወጡት አዋጅ መሠረት፣ ባንዲራው ላይ ያረፈውን ኮከብ እንኳ ማስከበር አልቻሉም፤ ወይም አልፈለጉም። አስተማሪም ለሚሉት ህዝብ እንኳ

ማስረዳት አልቻሉም። ፎርጂድ ገንዘብ እንጂ ፎርጂድ ባንዲራ አያስደነግጣቸውም። ለኮከቡ የሰጡት ትርጓሜስ አይገርምምን? ከመቼ ወዲህ ነው ኮከብ እኩልነትን ወክሎ የሚያውቀው? ይህን ወይቅ የሚያውቅ ይኖር ይሆን? ሉአላዊነትን ይወክላል ቢባል እንኳ ትንሽ ሲያሳምን ይችል ይሆናል። በሲሉች ሀገራት ባንዲራ ላይ ኮከቡ ቢታይም ትርጉሙ እንደኛ ሀገር አሻሚ አይደለም። ለአፍሪካ የባንዲራ ቀለም ያደለች ሀገር እንዲህ መሆንዋ ያሳዝናል! እንደሚታወቀው ኮከብ መበላለጥን እንጂ እቻ መሆንን ወክሎ አያውቅም። ትውልድ ዘላቂ የሆነ አይነኬ ምልክት ሲኖረው አንድነቱ ይጠናከራል፤ ተግባቦቱ ይቀጥላል። የስንት ዘመን ጥንታዊ ታሪክ ያላት ሀገር ባንዲራዋን በየጊዜው ስትለዋውጥ ያሳፍራል። ነገ የሚመጣው ደግሞ ባንዲራችን ላይ የሚያስቀምጠውን አናውቅም። በፓርቲ ባንዲራና በሀገር ባንዲራ መካከል ያለው ሰፊ ልዩነት ሳይገባቸው ቀርቶ አይመስለኝም። በዲሞክራሲ አመራሩ የሚል ፓርቲ ባንዲራው ላይ ጠብመንጃ ማስቀመጡ ገርሞን ሳያበቃ ፔንታግራሙን ባንዲራችን ላይ ሲያስቀምጡት ድፍረታቸው አላስደነገጣቸውም። ይህ ሳያበቃ ፔንታግራሙ የሲሰበትን ባንዲራ ማውለብለብ እንደሚያስቀጣ ሲለፍፉ ይደመጣሉ። ሆሊውድን ሳይቀር ዘልቀው በመግባት የአጂሉን ስርአት ትእዛዝ ለማስረፅ እየሞከሩ የሚገኙት ኢሉሚናቲዎች ምልክቶቻቸውን በተለያዩ ፊልሞች እንዲታዩ ይደረጋሉ። ፔንታግራም የተባለው ምልክታቸው ታዋቂ ነው፤ የራሱ የሆነ ትርጉምም አለው። ይህ ባለ አምስት ጫፍ ኮከብ የፍየሉ ጭንቅላት ሁለቱ ቀንዶቹ በሁለቱ ጫፎች ጆሮዎቹም በሁለቱ ጫፎች ገብተው አገጩ ከአንደኛውና ከቀሪው ጫፍ ተዘቅዝቆ ሲውል የሰይጣኒዝም ምልክት ነው። ኮከቡ በክብ ውስጥ ሲገባ የኢ-አማኒነት (ፓጋን) ምልክት ነው። ሳናውቅ የምናደርገው በዛ። አውቀን የምናደርገውም ጠንዛ። የረጅም ዘመን ታሪክ ያለው ህዝብ እንዲህ እየቀለለ ሲመጣ ያስደነግጣል። ኢሉሚናቲዎች ይህን ታዋቂ ምልክታቸውን በእጅ አዙር ለጥፈውብን ይሆን? ለነሱ ምን ይሳናቸዋል? ከኛዎቹ መሪዎች ውስጥስ አባላቸው ቢኖር ያስገርማል? በዚህ የሚገረም ካለ ተገርሞ አያውቅም ማለት ነው። የኢሉሚናቲዎች ጠባይ ለገባው ይህን ቀርቶ ሌላ ቢያደርጉ አይገረምም። ጠባያቸውን በጥቂቱ ልጠቃቅስ።

ኢሉሚናቲዎች ከተለያዩ ድብቅ እውቀቶች ጋር ቢኖሩም ስለነሱ ማንም ምንም ቢል ውሸት ነው ማለት አመላቸው ነው። ለነሱ ውዥንብርና ተረት እንጂ ሌላ አይደለም። ኢሉሚናቲዎች በሁሉም ድርጅቶች ውስጥ መሰግሰግ ተግባራቸው ነው። በቤተ ክርስቲያናት ውስጥ፣ በፖስታ ቤት ውስጥ፣በተለያዩ የመገናኛ ድርጅቶች ውስጥ፣ በትናንሽ ግሮሰሪዎች ውስጥ ሳይቀር መሰግሰግን ያውቁበታል። በየትኛውም ቦታ አሰጡን ወኪሎች አሉአቸው። እነዚህ ወኪሎቻቸው ግን

የሚሰበሰቡትን መረጃ ለማን ሪፖርት እንደሚያደርጉ አያውቁም:: ዋና ዋናዎቹ በማህበረሰቡ ውስጥ ራሳቸውን ቀብረው መረጃውን እስኪመነትፉ ይጠባበቃሉ::

ኢሉሚናቲዎች የጠፈር ምርምሮችን በማድረግ ካቅማቸው በላይ እየሰሩ ነው:: የሰው ልጅ ወደ ሌሎች ዓለማት መሠራጨት ከጀመረ ሌሎችን ዓለማት በመቆጣጠር የመጀመሪያዎቹ በመሆን በዚያም ስራጊ ፈጣሪ መሆን ይፈልጋሉ:: ለእነርሱ ዓላማ አስፈላጊ የሚሆኑ ልዕለሰቦችን በላቦራቶሪ ሳይቀር በማምረት ላይ ናቸው::

ኢሉሚናቲዎች ዘመናዊ ቴክኖሎጂን የታጠቁ ናቸው:: የተራቀቁ ኮምፒዩተሮች ባለቤቶች ጭምር:: በቤተ ሙከራዎች ምርምር ማካሄድ የሰው ልጆችን ያርዳሉ:: ምስጢራዊ መልእክቶችን በአየር ሞገዶችና በጋዜጣ መጣጥፎች ውስጥ ይለዋወጣሉ:: በዜና ዘገባዎች ሳይቀር ቀብረው ይደማመጣሉ::ሌሎች እንግዳ የሆኑ ምስጢራዊ ግንኙነቶችንም ያደርጋሉ:: በልብሶቻችን ሳይቀር መረጃ ይለዋወጣሉ::

የሰዎችን አእምሮ ከፍ የሚያደርጉ ሰዎች እንዲቀጥሉ አያደርጉም:: በትምህርት ቤቶች በመሰግሰግ ወጣቶች ሳያውቁት እንግዳ የሆኑ ሙዚቃዎችን እንዲያደምጡና ምልከታቸው ያረፈበት አለባበስ እንዲኖራቸው ያደርጋሉ:: አዲሱ ትውልድ እንቅስቃሴ ንቁ ሆነው ይጠብቅ ዘንድ በአእምሮ የመጠቁ ወጣቶችን ይመለምላሉ:: ለኢሉሚናቲዎች በሚሊዮን የሚቆጠር ገንዘብ ምናቸውም አይደለም::

በተቃዋሚ የፖለቲካ ድርጅቶች ሰርገው በመግባት አለቃ ይሆናሉ:: በወቅቱ ባለው ሥርዓት ውስጥም መሪዎች ይሆናሉ::አስፈላጊ ሆኖ ያገኙትን ወደ ሥልጣን ያመጣሉ:: ግድያ ጥንታዊ የፖለቲካ መሳሪያቸው ነውና ተክነውበታል:: ከብዙ አስገራሚ ግድያዎች ጀርባም አሉበት::

ጦርነትን የሚያደርጉት የኢሉሚናቲ ቡድኖች አንዱ ሌላውን አልታዘዝና አልደራደር ሲል ነው:: ጦርነት ውድና አክሳሪ መሆኑን ቢሰብኩም ለነሱ ጥቅም አስፈላጊ ሆኖ ካገኙት ያደርጉታል:: የመንግሥታትን ትኩረት በውስጣቸው ከለገለጉት ለባይ ላይ ዞር ለማድረግ ሲሉ ሌላ የፖለቲካ አለመረጋጋትና አመፆችን ይፈጥራሉ::

አዳዲስ የጦር መሳሪያ የሚፈበርኩበት ምስጢራዊ ላቦራቶሪዎች አሏቸው:: ገዳይ በሽታዎችን እንደጠመንጃ በመጠቀም እምቢተኞችን ይቀጡበታል:: ተፈጥሮን

በመቆጣጠርና በማዘዝ ተግራሪዎቻቸውን ለማንበርከክ በመመራመር ላይ ናቸው። በቀጣይ ከፍተኛ ሞገዶችንና ጨረሮችን በመጠቀም የመሬት መንቀጥቀጥን፣ እሳተ ገሞራን፣ ጎርፍን፣ ሱናሚንና ድርቅን በመፍጠር እምቢተኞቻቸውን ለመቅጣት በመዘጋጀት ላይ ናቸው።

ታሪክን መልሰው በመፃፍ ለስማቸው አገልግሎት እንዲሰጥ ያደርጉታል። ለምሳሌ በትምህርት ቤቶች ስለኢየሱስ ክርስቶስ ሳይቀር ታሪካዊ ማስረጃ እንደሌለ በማስመሰል የተማሪዎችን አእምሮ በብዥታ ይሞሉታል። እነሱ ያልፃፉት ታሪክ ታሪክ አይባልም። ታሪክን የራሳቸው የማድረግ መመብትም በእጃቸው ነው።

ዜና ማሰራጫዎችን ይቆጣጠራሉ። የዛሬውን ጧት ዜናም መስማት በምትፈልጉት መንገድ ሳይሆን እንድትሰሙት በሚፈልጉበት መንገድ ቀምረው ያቀርቡላችኋል። ማንኛውም ከነሱ እንቅስቃሴ ጋር የማይጣጣም ድርጊት ወይም ትኩረት አያገኝም አይያም ይታፈናል። ቴሌቪዥንን መቆጣጠር ዋነኛ ስራቸው ነው። ጣፋጭና አስቂኝ ቀልዶችን በማስተባባፍ በአእምሮ ከረሚሳዎች የሰዎችን አእምሮ በጥልቅ እንዳያስብ ያደርጉታል። ለመቆጣጠር ካሳቃታቸው በቀር፣ ወይም ትኩረት ካልነፈጉት በቀር፣ ወይም የሚገነባው ንቃተ ህሊና ኢምንት ሆኖ ካላገኙት በቀር የትኛውንም ቴሌቪዥን ፕሮግራም አይምሬትም አይስቱትም- አቅም አንሶት -ትንፋሽ እጥረት እስኪያጣጥር ማንቁርቱን ይዘው ይገድሉታል።

ኢሉሚናቲዎች የአለምን ስቶክ ማርኬት ከመቆጣጠር አይቦዝኑም። የዓለም የገንዘብ ፍሰትም በነሱ ቁጥጥር ስር ነው። የገንዘቦች ምንዛሬም በነሱ ፍላጎት ብቻ የሚወጣ የሚወርድ ይሆናል። የነሱ ባልሆኑ ድርጅቶች መካከል ተቀናቃኝነትን ይፈጥራሉ። እነሱን የማይተባበሩትን ዋጋ አልባና እብድ እንዲሆኑ ያደርጓቸዋል።

በመላው ዓለም የኃይል እጥረት እንዲኖር ይፈልጋሉ። ብዙ የኃይል ምንጮች ቢኖሩም ዓለም ያንን ተጠቅሞ ከነሱ ቁጥጥር ውጭ እንዲሆን አይፈልጉም። ነፍሱን ሳይቀር በፌኛ መሸጥ ይፈልጋሉ።

ሰዎች ስለ ኢሉሚናቲ እንዲቀልዱና እንዲያወሩ ቢፈቅዱም ጠለቅ ያለ ምርምሮችን አድርጎ ወደ አፍንጫቸው የተጠጋን ግን ማንቁርቱን ይቆርጡታል። ለዚህም አገልጋዮቻቸው ሰብአዊ ባህርያቸውን ወደ አረመኔ ፍጡርነት የለወጡ ናቸው።

ሲራኮስ የአባቱን ማስታወሻ ማቆም ባለመቻሉ ራት ምሳውን መዘጋጋቱን አላወቀም:: የድካም ስሜት ቢጫነውም የምስጢራዊ ማህበረሰቦች መንደርደሪያ አድርጉ የጀመረው የአባቱ ማስታወሻ፣ ኢትዮጵያ ውስጥ ወደ ተቋቋመው የምስጢር ድርጅት እስኪያዘልቀው ድረስ ንባቡን መግታት አልቻለም:: አሁን የደረሰበት ገፅ የህቡዕ ድርጅቶችንና የሊሎችን ገፅ እንቅስቃሴዎች የሚያዘወትሯቸውን ምልክቶችና ምስሎች የሚገልፀው ገፅ ላይ ነው:: ምልክቶቹን አንድ በአንድ ተመልክቶ ሲጨርስ ወደ ዋናው አንገብጋቢ ጉዳይ መድረሱን ተገነዘበ:: ይኸውም የአንድ፣ ኢትዮጵያ ውስጥ የተቋቋመ ህቡዕ ቡድን ምስጢር ተዘክዝኮ በማየቱ ነው::

# ፲፱

## ሱሉልታ፥ኢትዮጵያ

ከባህር ወለል በላይ ሁለት ሺህ አምስት ማቶ ከፍታ፣
ሱሉልታ። ጌራ ወደ ምዕራብ በመመልከት ላይ ነው። ፀሐይዋ
ከእድማሱ ጥግ እንኮይ መስላ ተንጠልጥላለች-ጥቁቁር
ዳመናዎችን ከላይ ተሸክማ። እልፉ እልፉ እንደምትሳም
ልጃገረድ የደመና ሽፋኗን እየከደነች ትስለመለማለች። ጌራ
ይህች እንኮይ ተንጠልጥላ እንድትቆይ አልፈለገም። ለዘላለሙ
እይሁን እንጂ ላሁኑ አንዱ እረኛ ከተንጠለጠለችበት ላጥ አርጉ
ቢሰለቅጣት ምኞቱ ነው። አዋዋሉ አሳር ሆኖበት ነበር። ሰማዩ
ከመዳመን ደመናው ከመነፍረቅ ሳይቆጠቡ ውለዋል። ቁስሉም
ሲያንገበግበው ነበር የዋለው። ምሽቱን ሲናፍቅ ፀሐይም ቶሎ
መግባቷን ትታ ስትሽኮረመምበት ነው የዋለችበት። ለእሱ
ወጥታ ለእሱ የምትጠልቅ መሰለችው። ጕፈሬያቸውን እንደ
ፋኖ የከፈከፉት የሱሉልታ ተራሮች፣ በላያቸው በሚጕማለሉት
የጉም ጋቢዎች ሸፍነው ባይደብቁት ኖሮ፣ እንደ ፋኖስ
ተንጠልጥላ ስትጨላሞስ የዋለችው ፀሐይ ግን፣ ሽርፍራፊ ብርሃኗ
ብቻ እሱን ለማስያዝ በቂ ነበር። ሆኖም መግቢያዋ እየቀረበ
ነው። ጌራም ፀሐይዋን በዓይኖቹ ገፍቶ ያስገባት ይመስል
ቁልቁል እየናጣት ነው።

ሱሉልታ በተራሮች የተከበበች በደኖች የተጀቦነች ስፍራ ብቻ
አይደለችም። የብርቅዬ አእዋፋት መገኛ አድባርም ናት።
በየእመቱ አያሌ የወፍ አድናቂዎች ይተሙባታል። ከሱሉልታ
ተራሮች እብራክ የሚንፎለፎሉት ጥርት ያሉ ምንጮች
የሙገርን ወንዝ ይቀላቀላሉ። ሙገርም በተራው ገባር
ምንጮቹን ሰብስቦ ወደ ሰሜን ምስራቅ ይጓዝና ታላቁን የአባይን
ወንዝ ይቀላቀላል።

ክረምት በመሆኑ የሱሉሉታ ረባዳ ሜዳዎች እንደተለ ሜዳው ውሃ
ቆሞባቸዋል። አረንጓዴ ስጋጃ የተነጠፈበት በሚመስለው

በኡሉልታ ሜዳ ላይ ጨሌ ሲግጡ የዋሉት ከብቶች በእረኛ ቶጪት ታጅበው ወደየበረታቸው በመነዳት ላይ ናቸው፡፡ ጌራ ለማጠናት የዋለችው ፀሐይ ጠልቃለች፡፡ ኒቃቡን አስተካከሉ፡ መከናነቢያውን፡፡ ፊቱም ሙሉ በሙሉ መሸፈኑን አረጋገጠ፡፡ አባያውንም በቁመቱ ልክ ለቆ ቆመ፡፡ ጥቁር በጥቁር፡፡ ጌራ አለባበሱን በትክክል ለመልበሱ እርግጠኛ ነው፡፡ አስቸጋሪ የሆነበት አረማመዱ ነው፡፡ እንደቆሰለ አውሬ እያጠለቀሰ ሲራመድ፣ የተደፈረች ሴት አካሄድ ስለመሰለው መንገዱ ላይ ጠያቂ እንዳያጋጥመውና ጉድ እንዳይሆን በልቡ ፀለዩ፡፡

# ፳

## በተራራው ከርሰ ምድር ውስጥ፥ጣቅርን

ሚራዥና ሻንጊዳ ሚራዥ ቢሮ ውስጥ በመወያየት ላይ ናቸው፡፡ ከሰዓታት በኋላ በሚደረገው ስብሰባ ላይ የሚቀርቡት ጥናቶች ተሰናድተው ተጠናቀዋል፡፡ ከጥናቶቹ ውስጥ አካባቢውን የሚገልፁ፣ የከበባችውን ኃይል የሚመለከቱ፣ ከበባውን ሰብሮ ለመውጣት የሚያስችሉ ጥናቶች ወዘተረፈ ሲሆኑ፣ የኢትዮጵያን የደህንነት መስሪያ ቤት አቋምና የዴርቶጋዳን ሁኔታ የሚገልፀው ጥናት ደግሞ በሚራዥ ተዘጋጅቶ ይቀርባል፡፡

ሚራዥ በአክሎግና በአያና ሁኔታ ላይ ሥጋቱ እየጠናበት መጥቷል፡፡ ደመነፍሳዊ ሥጋቱ ከምን እንደመነጨ ግን ሊረዳው አልቻለም፡፡ ባለፈው እንደተረዳው አክሎግ "ኢንጂነር ሻጊዝን ይገቡ እደራደራለሁ" የሚል አቋም በማንፀባረቅ ክፍልሚያው ይልቅ ድርድሩን አበክሮ የመረጠ ሰው ነው፡፡ ሚራዥ ይህን ለጥርጣሬው መነሻ ለማድረግ በቂው እንዳልሆነ አምኗል፡፡ ምክንያቱም ኢንጂነር ሻጊዝ ራሱ እንደራደር የሚል አቋም ስለነበረው ነው፡፡ ሻጊዝ እንደራደር ሲል "በምን" የሚለውን ያልገለፀ ከመሆኑ በቀር በአቋም ከአክሎግ ጋር አንድ ነው - ያው "እንደራደር" ባይ ነውና፡፡ የሁለቱን አቋም ልዩ የሚያደርገው አክሎግ ለሚራዥ ሹክ ያለው አስደንጋጭ መደራደሪያ ነው- ኢንጂነር ሻጊዝን እንደ ክርስቶስ አሳልፎ መስጠት፡፡ ለሚራዥ ይህ የማይሞከር ነገር ነው፡፡ ጥርጣሬ ያጫረበትም የአክሎግ "እንደራደር" የሚለው አቋም ሳይሆን "እንደራደርበት" ያለበት ጥቅም ነው፡፡ የድርጅቱ መንፈስ ያደረበት ሰው ሊያውም የድርጅቱ ማዕከላዊ ኮሚቴ አባል የሆነ ሰው ጓደኛውን ይዞ ለመደራደር ማሰቡ ሚራዥን አስደንግጦቷል፡፡ ማስደንገጥ ብቻም ሳይሆን እንዲጠራጠረው አድርጐታል፡፡ በሌላ በኩል የአያና ተፈሪ ሁኔታም አሳስቦታል፡፡

እያና በድርጅቱ ጉዳይ ላይ ለዘብተኛ እየሆነ ከመምጣቱም በላይ በተለይም የማዕከላዊ ኮሚቴው አባል ከሆነ ወዲህ ድርጅታዊ ስሜቱ እንደ ውሻ አፍንጫ እየቀዘቀዘ መምጣቱን ሚራዥ ልብ ብሎታል። እያና የማዕከላዊ ኮሚቴው አባል ከመሆኑ በፊት እንደ እርሱ ዴሞክራሲያዊ ስሜት ቃልም ሆነ ድርጅት የሚያስበው ሌላ ሰው የሌለ ይመስል ነበር። እንደ እያና ለዚህ ድርጅትም ሆነ በትራራው ውስጥ ለማደረጉ ምርምሮች የሚጨነቅ ያለ እስከማይመስል ድረስ የሚራራጥ ሰው ነበር። ይህን ሰው ድርጅቱን አሳልፎ ይሰጣል ብሎ መጠራጠር ጠርጥሮም ለሌሎች ማስጠርጠር ከባድ እንደሆነ ለሚራዥ ግልፅ ነው። በዚህ ትራራ ውስጥ የሚገኝ ሁሉ እያናን የሚያውቀው ለድርጅቱ የፅዳት ሠራተኛ ሆኖ እንኳ ቢሰራ ቅር የማይለው እንደሆነ ነው። እንደ ሚራዥ ሁሉ እያናና አከሎግን በጥርጥር ዓይን የሚመለከታቸው ሳዶፍ የተባለው አባል ነው።

ሳዶፍ ከመመልመሉ በፊት በሲ.አይ.ኤ ውስጥ ምርጥ አልሞ ተኳሽ ሆኖ መሥራቱም ብቻ ሳይሆን በስለላው ዓለም የበሰለ ልምድ ያለው በመሆኑ ሁለቱን ሰዎች ሲጠራጠር ከመሬት ተነስቶ እንዳልሆነ ሚራዥ ገምቷል። ስልኩን አንስቶ ወደ ሳዶፍ ቢሮ ደወለ።

ከደቂቃዎች በኋላ ሳዶፍ እያፏጨ ወደ ሚራዥ ቢሮ ገባ። ማፏጨት ልማዱ ነው። ለምዶበት ፉጨቱ ሲበዛ ሁሉ ያመልጠዋል።

"...በቃ እንደ ጥጃ እረኛ በየግድሙ ማፏጨትህ ልማድ ሆኖ ቀረ አይደል!?" አለው ሚራዥ የሚቀመጥበትን ወንበር ባገጩ እያመላከተው።

"ፉጨት የእረኞች ማስቲካ ነው።" ሳዶፍ ፈገግ አለ። "ፉጨት የማያልቅ ወጪ ቆጣቢ ማስቲካ ነው። ፉጨት በአንድ ጉዳይ ላይ እንድንመሰጥ ያደርገናል። ድርጅቱ የማስቲካ የሚችለኝ ከሆነ ፉጨቴን እተዋለሁ።" ማስቲካ ድርጅቱ

"ለዚህ ሁሉ ፉጨትህ ምትክ የሚሆን ማስቲካ ድርጅቱ ከየት ያመጣል? እንደለመድከው ፉጨትህን ቀጥል። አልሞ ተኳሽ ማፏጨቱም ሆነ ማስቲካ ማኘኩ ኢላማውን አያስተውም?"

"ሚራዥ. . . እኔ የማፈጨው ሳስብ ነው እንጂ ሳልታ አይደለም፡፡"

"ይሄ ልማድህ ግን ስታልምም እንዳያመልጥ እሲጋልሃለሁ፡፡ ለማንኛውም አሁን የፈለግንህ ስለ አያና እና ስለ አክሎግ አንዳንድ ጉዳዮችን እንድናወራ ነው፡፡ ባለፈው ነገሩን ጀምረህልኝ ነበር፡፡ ጆሮ ያልሰጠሁህ በችኮላ ነገር እንዳናበላሸ ብዬ ነው፡፡ ሁለቱን ሰዎች አንድ የሚያረጋቸው ነገር ብዬ ልትነግረኝ ስትል ነው በቆምክበት ትቼህ የሄድኩት፡፡ ከይቅርታ ጋር ካቆምክበት ጀምረህ ብንነጋገርስ? የዣንጊዳ መኖሩም ነገሩን በጉዳዩ ላይ የጋራ አቋም ለመያዝ ወሳኝ ነው፡፡ ሁለቱን ሰዎች አንድ የሚያደርጋቸው ምንድን ነው?" ሚራዥ ለሳዶፍ ጥያቄውን አሻግሮ በአትኩሮት ተመለከተው፡፡

ሳዶፍ ጥቂት ካሰበ በኋላ "ሁለቱን ሰዎች አንድ የሚያደርጋቸው...ሁለቱም ስማቸው በ'አ' መጀመሩ ነው፡፡" ብሎ ሚራዥንና ዣንጊዳን አፈራርቆ ተመለከታቸው፡፡ ሁለቱም እየሳቁ ነበር፡፡ እየቀለደ መሆኑ ቢገባቸውም ቀልዱን ትቶ ወደ ቁምነገሩ እንደሚሸጋገር በማመን፡፡ ሳዶፍ ቀጠለ፤ አልሳቀም፡፡ "ልክ በእናንተ በሁለታችሁ ስም ውስጥ የ 'ዠ' ፊደል ዘር እንዳለ ሁሉ፡፡ አክሎግና አያና በ'አ' አንድ እንደሆኑ እንዲሁ ሌሎች አንድ የሚያደርጓቸው ጉዳዮችም ሳይኖሩ አይቀሩም፡፡ ሚራዥና ዣንጊዳም እንዲሁ፡፡"

"አትቀልድ" አለ ሚራዥ እጁን አወናጭፎ፡፡ "ጊዜው የቀልድ አይደለም፡፡"

"ጊዜውማ የቀልድ መሆኑን ልታውቅ ይገባሀል" ሲል ሳዶፍ ቅጭም አለ፡፡ "በየሲኒማ ቤቱ ብትሔድ ቁም ነገር ተኮር ፊልምም ሆነ ቴአትር ተመልክተህ መውጣት አትችልም፡፡ ሀገሪቷ በቀልድና በስላቅ ተሞልታለች፡፡ ያሳሳቀ ሲኒማ ሲኒማ መባሉ ቀርቷል፡፡ እንኳንስ ሲኒማው ወጣቶች እንኳ ካሳሳቁ ጓደኛ መያዝ አልቻሉም፡፡

"እባክህ ያለን ጊዜ አጭር ስለሆነ ወደ ዋናው ሀሳብህ ብትገባ...." ዣንጊዳ ተቁነጠነጠ፡፡ ሳዶፍ ግን ቀጠለ፡፡

"...መላው ኢትዮጵዊ ሁሉ፣ ወደ ኮሚክነት እየተለወጠ ነው፡፡ ጠቅላይ ሚኒስትሩ ሳይቀር ፓርላማውን ከፊት ለፊት ተቀምጠው ማሳቅ ሥራቸው ሆኗል፡፡ እዚህ አገር ያሳሳቀ ወግ፣ ወግ አይባልም፡፡ መቼስ መሳቅ መልካም ነው፡፡ ነገር ግን

ትውልዱ ለምን ይስቃል ብለህ ብትጠይቅ የሚያስቀው ነገር አግኝቶ እንዳይመስልህ፡፡ 'ማሽላ እያረረ ይስቃል' እንዲሉ ውስጡ እያረረ እንደፈንዲሻ ጥርሱ ይስቃል እንጂ የሚያስቅ ጉዳይ ተገኝቶ አይደለም፡፡ የሚሳቅበት እየፈለገ፣ እየገባ ይስቃል፡፡ ትውልዱ ግራ ስለተጋባ፣ ለችጋሩ መላ ስላጣ፣ የኑሮ ውድነቱም ሆነ ተስፋ አስቆራጩ ሁኔታ ሰቀልድና ስሳቅ ሳይዳርገው አልቀረም፡፡ ውሃ ሲወስድ እያሳሳቀ ነው' እንዲሉ እያሳሳቀ የሚወስደው ውሃ ሙላት ኖሮም ይሆናል፡፡ ሳቅ ፍለጋ በየሲኒማ ቤቱ የሚሰለፈው ሁሉ ወዶ እንዳይመስላችሁ፡፡ በሳቁ የሚጎፋፍናት፣ በሳቁ አከናንቦ የሚያስተኛት፣ በሳቁ የሚያባብላት የውስጥ ቁማታ ስላለችው ነው፡፡ በሳቁ የሚያልፋት ቀን ስላለችው ነው፡፡ ሳቅ ብቻ አይደለም የበዛው፣ ካቲካላም ጭምር ነው፡፡

"አዳሜ በንቂስ እየወጣ ካቲካላ ቤቶችን ሲያጨናንቅ የሚያመሸው ወዶ እንዳይመስላችሁ፡፡ በመጠጥ እንደ ሽንፍላ ታጥቦ የማይጠራ ችግሩን አጠባ ነው፡፡ ማዳመጥ የማይፈልገውን ችግር ማርጠቢያው እና መጥረቢያው ያው ካቲካላ ብቻ በመሆኑ ነው፡፡ ነገር ግን እስከ አሁን በዚህ ሁኔታ የተፈታ ችግር የለም፡፡ የበረዶው አካባቢ ኗሪ ብርዱን ለመታገስ ካቲካላውን ሲጎነጭ፣ የዚህ አገር ነዋሪ ግን የጠርሙስ አንገት የሚያንቀው ችግሩን ያስታገሰ መስሎት ነው፡፡

"አብዛኛው የችግሩ ምንጭ ምን እንደሆነ ለማወቅ አልታደለም፡፡ ሰርክ ካቲካላ የሚቀመቅመው ውሉንና ስሩን ለማያውቀው ችግሩ ነው፡፡ ሁላችንም የችግሩን መገለጫዎች እንጂ የችግሩን ምንጭ ለማየት አልቻልንም፡፡ ሆኖም…… ችግሩን በትክክል ያላወቀ መፍትሔውን ሊያገኝ አይችልም፡፡ ማንኛውም መፍትሄ የሚመነጨው ከራሱ ከችግሩ ነው፡፡ ነገር ግን የኢትዮጵያ ችግር ወደ ችጋርነት ተሸጋግሯል፡፡ የችግር ከፍታው ችጋር ነው፡፡ ችግር ለዘመናት እንደ ኩሶ ተጣብቶ ሲኖር ወደ ችጋርነት ያድጋል፡፡ የኢትዮጵያ ችግር፣ ችጋር እንጂ ችግር አለመሆኑን፣ መገንዘብ ያስፈልጋል፡፡ የትናንሽ ችግሮች ምንጭ ሆኖ የሚያገለግለውም ይኸው ለዘመናት የጠናብን ችጋር ነው፡፡ ጊዜያዊዉን ችግር እንጂ ዋናውንና የችግሮቻችንን ሁሉ እውራ የሆነውን ችጋራችን የተረዱት ጥቂቶች ናቸው፡፡

"ብዙ ሳንርቅ የኛውን ድርጅት እንደ ምሳሌ መውሰድ እንችላለን፡፡ ዴርቶጋዳ ዋናውን ችጋሩን ከሥሩ ለመመንገል ሲል ጥቃቅን ችግሮችን ችላ እያለ ሲያልፍ እያየን ነው፡፡ የዚህንም ዋጋ በገፍ እየከፈለ ነው፡፡ ጥቃቅን ችግሮች በየዘርፉ እየተመነደጉ ራሳቸውን በመቻል ወደ ችጋርነት በመለወጥ ላይ ናቸው፡፡ ድርጅቱ በለዘብተኝነት ያለፋቸው እያሌ ችግሮች እንደ ጻዋ ሊውጡት ተቃርበዋል፡፡ አሁን ትንቅንቁ በጥቂት ቡቃያዎችና በእያሌ አረሞች መካከል ነው፡፡ አንዛዛ አትብሉኝ እንጂ በድርጅታችን ውስጥ ከቡቃያዎች ይልቅ አረሞች እንደበዙ መገንዘብ ቀላል ነው፡፡ የመጀመሪያው ዴርቶጋዳ ከፈነዳ ወዲህ፣ ድርጅቱ በለዘብተኝነት ያለበቂ ጥናት ያስገባቸው አባላት ድርጅቱን አሳልፈው ሰጥተውታል፡፡ ከነዚህ ከሀዲዎች ውስጥ አክሎማ እና አያና የሌብትም ማለት ቁልነት ነው፡፡" ይህን ብሎ ሲያበቃ ሳዶፍ ሚራዥንና ዣንጊዳን አፈራርቆ ተመለከታቸው፡፡ ባንዛዛው ንግግሩ የተሰላቹ መስሎት ነበር፡፡ እነሱ ግን በጥሞና እየተከታተሉት መሆኑን አጤነ፡፡

"አሁን ወደ ዋናው ቁም" ነገር መጥተናል፡፡ ለመሆኑ የጥርጣሬህ ምንጭ ምንድን ነው?" ሲል ዣንጊዳ ሳዶፍን ጠየቀው፡፡

"በሁለቱም ክንዶች ላይ ተመሳሳይ ምልክት አይቻለሁ፡፡"

"ምን አይነት ምልክት?"

"ሁለቱም የጉሽ ቀንድ ቅርፅ ያለው ንቅሳት አላቸው፡፡"

"ማለት…"

"ወረቀትና ብዕር ብታቀብለኝ ስዬ ላሳይህ እችላለሁ፡፡" ሳዶፍ ከሚራዥ ወረቀትና ብዕር ከተቀበለ በኋላ በችኮላ በሁለቱ ሰዎች ላይ የተመለከተውን ምስል ጫርጫር አድርጎ ጠረጴዛው ላይ አስቀመጠው፡፡ ሚራዥና ዣንጊዳ በመገረም ምልክቱ ላይ አፈጠጡ፡፡ ያለ አንዳች ንግግር ምልክቱን ብቻ ሲያጤኑ በየግላቸውም እያሌ ሀሳቦችን ሲያነሱ ሲጥሉ ቆዩ፡፡

"የስብሰባው ሰዓት እየተቃረበ ነው" በማለት ሚራዥ ፀጥታውን አደፈረሰው፡፡ "እነዚህ ሰዎች......." ብሎ ሳይጨርስ ዣንጊዳ አቋረጠው፡፡

"በስብሰባው ላይ እንዳይካፈሉ ለማለት ፈልገህ ነው? ተሳስተሃል፡፡ ስብሰባውን ይካፈሉ፡፡ እንደተጠራጠርናቸው ከወዲሁ ከተረዱ ነገር ተበላሸ ማለት ነው፡፡ ከዚህም ሌላ እኛ

ብቻ የማዕከላዊ ኮሚቴ አባል የሆነን አባል የማገድ ስልጣን የለንም፡፡"

"እቅዳችንን ከተረዱ..." ሚራዥ እንደገና ሊናገር ሲል ሳዶፍ ካፉ ላይ ነገሩን ቀማው፡፡

"ብስብሰባው ላይ የሚቀርቡት አካባቢንና ሁኔታዎችን የሚገልጹ ጥናቶች ናቸው፡፡ አንዳንድ ጉዳታቸው ከፍረኛ ይሆናል ብዬ አልገምትም፡፡ ቢሰሙአቸው ላይ እንዳይገኙ በማድረግ ከምንከስረው ኪሳራ የላቀ ኪሳራ እንከስርም፡፡ ከነሱ ጀርባ ያሉትን እጆች እስክናውቅ፣ በጥንቃቄ ጉዳያቸውን መያዝ አለብን፡፡ ከዚህ ባተጨማሪም አያና ራሱ በስብሰባው ላይ የሚያቀርበው ጥናት ስላለው የሚያቀርበውን ጉዳይ መስማቱ ጥቅም አለው፡፡

"ሳዶፍ ያለን ጊዜ እጅግ አጭር ነው፡፡ በዚህ አጭር ጊዜ ከነሱ ጀርባ ያለውን እጅ እስክናጠና የከበባው ሰለባ እንሆንም" ሚራዥ ሳዶፍ ከሳለው ምልክት ላይ ዓይኖቹን ለመንቀል አልቻልህ አለው፡፡

"አውቃለሁ ረፍዶብናል፡፡ ... ነገር ግን ከሚመሽብን ቢረፍድብን ይሻላል፡፡" ይህን እየተነጋገሩ ባሉበት ቅፅበት የስብሰባው ሰዓት ደርሶ ነበር፡፡ ሶስቱም የሚራዥን ቢሮ ለቀው ወደ ስብሰባው አዳራሽ ሲገቡ ለሁለት ደቂቃ ያህል ዘግይተው ነበር፡፡ አክሎማንና አያናን ወደስብሰባው ቀድሞ በመግባት የቀደማቸው አልነበረም፡፡

# ፳፩

ኪራኮስ የአባቱን ማህደር ካገኘው ጊዜ ጀምሮ ማንበቡን ቀጥሎበታል፡፡ የአባቱ ማስታወሻ፣ የዓለም አቀፍ ምስጢራዊ ማህበረሰቦችን ታሪክ ባጭሩ ካስቀመጠ በኋላ፣ አፍሪካ ውስጥ ብሎም ኢትዮጵያ ውስጥ የፈፀሙትን ደባ መተንተን ገብቷል፡፡

ምዕራባውያን በኢሉሚናቲዎች እየተመሩ ሶስት ጊዜ ዘረፉን፡፡ በመጀመሪያ ሰላዮቻቸውን በመላክ ዕውቀቶቻችንን ዘረፉ፡፡ ኢትዮጵያ ውስጥ በዚህ ተግባር ሰተት ብለው ከገቡት እውቅ ሰላዮች መካከል ቫስኮ ደጋማንና ጀምስ ብሩስን መጥቀስ በቂ ነው፡፡ ከነሱ በፊትም ሆነ በኋላ የመጡት ተግባራቸው ይኸው ነበር ዕውቀት ዘረፋ፡፡ ማወቃቸው ደግ ነበር፡፡ ነገር ግን ዐዋቂዎቻችንና የዕውቀት ምንጮቻችንን ሁሉ ዘርፈው የራሳቸው አረጉ፡፡ እነዚህ ሰላዮች ዕውቀት ፍለጋ መጥተው ለቃቅመው ከመመለሳቸው በፊት ምዕራቡም ሆነ ምስራቁ ዓለም የሚለብሰው የሚቀምሰው የሚልሰው መናኛ ደሀ ከመሆኑም ባሻገር በዕውቀትም በሀብትም ምንዱብ ነበር፡፡

ከዚህ በኋላ ነበር ሁለተኛው ዘረፋ የተካሄደው፡፡ በዕውቀታችን ዕውቀቶቻቸውን ካደላደሉ በኋላ ቶሎ ቶሎ መርከቦቻቸውን ሠርተው ንብረት ዘረፋ መጡ፡፡ ባሪያ አርገው ሲያሠሩን እንደከብት እያሰሩ መርከቦቻቸው ላይ ጫኑን፡፡ በራሳችን እውቀት በሰራት ሠንሰለት ለሠሩን፡፡ በራሳችን እውቀት በሠራት መርከብ ለጋዙን፡፡ ጥቁር ጥቁሩ እየተመረጠ ተነዳ፡፡ ለምን ጥቁር ብቻ እየተመረጠ ተነዳ? ብሎ መጠየቅ ተገቢ ነው፡፡ ኢትዮጵያ ውስጥ ለሽያጭ የተነዳው ከደቡብ ኢትዮጵያ ነበር፡፡ በሰሜን ኢትዮጵያ የሠፈረው አብዛኛው ህዝብ ከእስራኤል ዘር ጋር ንክኪ ይኖረዋል ብለው በመገመታቸው ነው፡፡ ሲሳም የሞኝ እውቀት ነበራቸው ጥቁሮች የሰማይ ኃይላትና የምድር ሰዎች የደቀሏቸው ኔፍሊሞች ናቸው የሚል የጅል ሀሳብም ነበራቸው፡፡ ለነሱ ኔፍሊም የሆኑት ጥቁሮች ንብረትና ጥበብ ያላቸው ናቸው፡፡ ከፊል መልአክ ከፊል ሰው በመሆናቸው መላእክትን አስረው የሚያመራት ያህል ቀጠረት፡፡

ዕውቀትና ንብረት ዘርፈው አደበቃቸውም፤ ሶስተኛውን ዘረፋ አስከተሉ፡፡ በዕውቀታችንና በንብረታችን ከደረጁ በኋላ ዘገራቸውን ነቅንቀው፣ ጦራቸውን

ግላሰውብቸዋል፡፡ በኢሉሚናቲዎች ላይ መጻህፍት የጻፉ አንዳንድ ሰዎች እንደተገደሉ ማን ያስታውሳል፡፡ ሆኖም አንዱ የጻፉት ማስታወሻ ለማድያ የሚያበቃ ጉዳይ እንደሌለው አሰቧል፡፡

የኪራኮስ አእምሮ ብዙ ሀሳቦችን ሲያነሳ ሲጥል ከቆየ በኋላ የፈለበጠው ሀሳብ ሁሉ ነፋስ እንደመጣበት ጉም በፍጥነት እየተበተነ ሲያስቸግረው ንባቡን ከመቀጠል በቀር አማራጭ አልነበረውም፡፡ ወደ ዋናው ፍንጭ እየተቃረበ መሆኑን የተረዳው የሚቀጥለውን ምዕራፍ ማንበብ ከጀመረ በኋላ ነበር፡፡

ጋሡስ የሚባለውን ድርጅት ከዘጠኝ ሰዎች በቀር የሚያውቀ እንደሌለ ጥርጥር የለኝም፡፡ ከዘጠኙ አንዱም እኔ ነኝ፡፡ ምናልባት አስረኛ ሲሆን የሚችለው ይህን ማስታወሻዬን ያገኘ ሰው ብቻ ይሆናል፡፡

ኪራኮስ ትንፋሹ ሲፈጥን ተሰማው፡፡ማስታወሻውን ከድኖ ለመረጋጋት ሞከረ፡፡ ሆኖም ከድኖ መቆየት አላስቻለውም፡፡ እንደገና ማስታወሻውን ገለጠ፡፡ በቅደም ተከተል ማንበብ ተስኖት ዓይኖቹ ሁሉንም ቃላት አዳረሱ፡፡ አንድም ነገር ሊገባው አልቻለም፡፡ ትንፋሹን በረጅሙ ለቆ እንደገና ካቆመበት ጀመረ፡፡

ጋሡስ ስለሚባለው ድርጅት ማውራትም መነጋገርም ሆነ መፃፍ የተከለከለ ነው፡፡ ይህ የእኔ ማስታወሻ ጋሡስ ስለተባለው ድርጅት የተፃፈ ብቸኛው ጽሑፍ መሆን አለበት፡፡ ለምን እንደምናዝዝ ልቀጥላለሁ፡፡

ከጀርባዬ ኮቴአቸው እየተሰማኝ ነው፡፡ በዚህ ድርጅት ውስጥ አገልግሎቴ አብቅቷልና ሊገድሉኝ እንደሚመጡ እርግጠኛ ነኝ፡፡ ለምን እናዝዛለሁ? እውነት የምትገኘው ከንዝዚ ቃል ብቻ ሳይሆን ይቀራል? ወደ ቢላዋውና ወደ ማላውቀው አለም በጊዜ ለምርኩዛት ምድር አፍኝባት የምርኩትን ምስጢር ይዤባት ልሄድ አስገባም ብዬ አሰባለሁ፡፡ ከዚሁም ጋር ምናልባት ልጂ ይህን ማስታወሻዬን ቢያገኘው ራሱን ያድንበታል፡፡ ራሱን ብቻም አይደለም በዐቢ አምኚ በአሬ የከድኩትን ድርጅት ከመፈራረስ ያድንበታል፡፡ ተራራው ውስጥ ራሳቸውን እንደገናር ቀቀሱ የራሳቸውን ተዝካር በማውጣት የተደገሰውን ድግስ ምናልባት ይህ ማስታወሻዬ በልጂ ከንባ ሲነገራቸው ይችላል፡፡ ያተርፋችዋል ብዬ መገመት ግን ያዳግተኛል፡፡ ይህን ማስታወሻዬን ለልፎ ልጂ ከእኔ ጋር አልነበረም፡፡ ወደ

# ጃኖ

## ሱሉልታ + ኢትዮጵያ

አደገኛ አጥር ዙሪያውን የዞረውን ቪላ ቤት ፀጥታ ሰፍኖበታል፡፡ "አደገኛ ውሻ አለ"የሚል ማስፈራሪያ በጥቁሩ በር ላይ ተፅፎ ይታያል፡፡ ይህን ጥቁር በር አልፎ የሚገባም ሆነ የሚወጣ እከል ብዙ ጊዜ አይታይም፡፡ የዚህ ቤት ካርታና ፕላን የተያዘው በአንድ ዕድሜው ለስልሳ፣ ሁለት ፈሪ በቀረው የድርጅቱ ሰው ነው፡፡ አላገባም፣ አልወለደም፡፡ ምግብ ቀቃይ ሰራተኛም ቀጥሮ አያውቅም፡፡ ፈርጣማው ጥበቃ ወደዚህ ግቢ ያለ ትዕዛዝ ወፍ እንኳን አያስገባም፡፡ ጥበቃውም ሆነ የቤቱ አባወራ የድርጅቱ ሰዎች ናቸው፡፡

ጥበቃው ዛሬ እንግዳ ነገር ገጥሞታል፡፡ እንዷት በኒቃን ፊቷን የሸፈነች፣ አባያ እስከ እግር ጥፍሯ ያንበረሰሰች ሴት ከበር ቆማ እንዲያስገባት በመጠየቅ ላይ ናት፡፡

ይባስ ብላ እርጋታ በተሞላበት ሁኔታ በጎርናና የወንድ ድምፅ የቤቱ ባለቤት አበር ድረስ መጥቶ እንዲያናግራት ጥበቃውን ጠየቀች፡፡ ጥበቃው ግራ መጋባቱ ስፊ ፊቱ ላይ ይነበባል፡፡ ይባሱን ግራ ያጋባው የቤቱን ባለቤት የምስጢር ስም ጠርታ እንዲጠራላት መጠየቋ ነው፡፡

"ባለቤቱ ለስራ ጉዳይ ወጣ ብለዋል፡፡" ሲል ጥበቃው ፈርጠም ብሎ መለሰ፡፡

"ቤት ውስጥ እንዳሉ አውቃለሁ" አለች ሴቲቷ መጣደፏ እየታወቀባት፡፡ ከበር ብዙ መቆሟ ለአደጋ እንደሚያጋልጣት ተረድተዋለች፡፡ ባይጨላልም ኖሮ የዚህን ያህል የመቆሟ ትዕግስትም ሆነ ጊዜ ባልነበራትም ነበር፡፡

"ባለቤቱ ለሥራ ጉዳይ ከወጡ ሰንብተዋል፡፡"

"እዚህ እንዳሉ አውቃለሁ ጌታዬ፡፡ ላባ ከበር ቆማ እየጠበቀችህ ነው በልልኝ፡፡" ጥበቃው ዕየዋሻት እንደሆነ ተረድታዋለች፡፡ ሁኔታዋን ለማጣራት ጊዜ እየሸመተ እንደሆነም እንዲሁ፡፡

"ላባ?" ወጠምሻው ጥበቃ ይህን ቃል ሲሰማ ቀንዱን እንደተመታ ከብት በፍጥነት ፊቱን አዞረ፡፡ የግቢውን በር ጠርቅሞ ዘግቶባት ወደ ውስጥ ተመለሰ፡፡ ....... ከአፍታ ቆይታ በኋላ የግቢውን በር ከፍቶ ጥበቃው ወደ ውስጥ በፍጥነት ትተታት፡፡ በኒቃንና በአባያ ተሸፋፍና የቆመችው ሴት ማን እንደሆነች ከውስጥ ሰምቶ ተመልሷል፡፡ "ላባ" የሚለው የምስጢር ስም የጌራ መሆኑንም አውቋል፡፡

"ጌራ... ምን ተፈጠረ?" ጥበቃው ጌራ እያንከሰ ሲራመድ አንድ ችግር እንደተፈጠረ ገብቶታል፡፡

"ቀላል ነው፣ ለክፉ አይሰጥም፡፡"

በግቢው ውስጥ ሶስት መኪናዎች ቆመዋል፡፡ ጌራ ተገላምጠ መኪኖቹን አይቶ ወደ ሳሎን ዘለቀ፡፡ ሳሎኑ ውስጥ ማንም አልነበረም፡፡ ጥበቃው ከፊት ለፊት እየመራ ወደ መኝታ ቤት ይዞት ገባ፡፡ መኝታ ቤት ውስጥም ማንም አልነበረም፡፡ መኝታ ቤቱ ውስጥ ከቆመው ቁምሳጥን ጥግ አንድ የልብስ መስቀያ የሚመስልና ከግድግዳው የወጣ ጉጥ ጥበቃው ወደ ቀኝ ሲጠመዝዘው የመኝታ ቤቱ ግድግዳ አፉን ከፈተ፡፡ ተከታትለው ገቡ፡፡ በዚህ ክፍል ውስጥ ሶስት ሰዎች በፀጥታ ቆመው የጌራን መግባት በመጠባበቅ ላይ ነበሩ፡፡ ከሶስቱ አንዱ የቤቱ ባለቤት ሲሆን ሁለቱ አዲስ አበባ ውስጥ የሚንቀሳቀሰው የዴርቶጋዳ ሴል አባላት ናቸው፡፡ ከዚህ በፊት ደጋግመው ተገናኝተዋል፡፡

ጌራ ሰላምታ ከሰጣቸው በኋላ ኒቃብና አባያውን አውልቆ የሆነውን አሳያቸው፡፡ የሜሮዳን መያዝ መስማታቸውንና እርሱ ግን የደረሰበት ጠፍቷቸው እንደነበር ከነገሩት በኋላ ቁስሉን ለማከም ርብርቡ ተጀመረ፡፡ የቤቱ ባለቤት በአዲስ አበባ ዙሪያ ለሚንቀሳቀሰው ህዋስ ተመድቦ እዚሁ ግቢ ውስጥ በሌላ ክፍል ተቀምጦ ለሚጠባበቀው የህክምና ቡድን ከመደወሉ፡ ለጌራ የህክምና ዕርዳታ የሚያደርጉ ሰዎች ወዲያውኑ ከች አሉ፡፡

ግርጻ ተግድላ ወደ ጥልቁ ገደል ስትወረወር በዓይን ህሊናው ታየችው፡፡ ዓይኖቹን በሁለት እጆቹ ጭዝ ቃቸው፡፡ ለመጀመሪያ ጊዜ የተስፋ መቁረጥ መንሸ ውስጡን ሲያምሰው ተሰማው፡፡

ጉባኤው ተጀምሯል፡፡ ጥናቶችም በመቅረብ ላይ ናቸው፡፡ አካባቢውን በሚመለከት ፅሁፍ የምታቀርበው እንስታ ወደ መድረኩ ወጥታ ወረቀቶቿን ካስተካከለች በኋላ ጉሮሮዋን ደጋግማ አጥርታ ገለፃዋን ጀምራለች፡፡

እንድም ወፍ ሳይቀር አካባቢውን አጥርታ ታውቀዋለች በመባል የምትቆለጳጰሰው እንስታ ከአስፈላጊው በላይ አካባቢውን ቁልጭ አርጋ ለማሳየት ቆርጣ የተነሳች ትመስላለች፡፡ ከፊት ለፊት ባለው ግዙፉ ስክሪን ገፅ ላይ የአካባቢውን መልክዓ ምድር የሚያሳየው ምስል ተገጭሯል- የሊቦ ከምከም አካባቢ፡፡

የሊቦ ገመገሞች ከጀርባ ከተገጩሩ በኋላ በተለያዩ ቀለማት የተፃፉ የቁጥር መረጃዎች መምጣት መሄድ ጀመሩ፡፡ የቁጥር መረጃዎቹ እንደሚያመለክቱት ያሉበት አካባቢ ከአዲስ አበባ በሥተሰሜን 652 ኪሎ ሜትር ርቀት ላይ ይገኛል፡፡ ከጎንደር ከተማ 85 ኪሎ ሜትር፣ ከባህር ዳር ከተማም 80 ኪሎ ሜትር ይርቃል፡፡ በስተደቡብ ፎገራ፣ በስተሰሜን በለሳ፣ በስተምስራቅ እብናት፣ በስተምዕራብ ጣና ሐይቅ በሚያዋስነው ሊቦ ከመከም በሚባል አካባቢ ከአዲስ ዘመን ከተማ 6 ኪሎ ሜትር ርቀት በሚገኝ ተራራ ላይ ናቸው፡፡ 1081 ያህል ስኩዌር ካሬ ሜትር ስፋት ያለው ይህ አካባቢ ከመቶ 21 እጁ ተራራማ፣ 42 እጁ ሜዳማ፣ 30 እጁ ወጣ ገባ ሲሆን አንድ እጁ ደግሞ ሸለቋማ ነው፡፡ የአየር ንብረቱ ደጋም ወይናደጋም የተቀላቀለበት ሆኖ ዘጠና በመቶ ደጋማ ነው፡፡ አማካኝ የሙቀት መጠኑም ከ11 እስከ 27 ዲግሪ ሴንቲ ግሬድ ነው፡፡ ከባህር ወለል በላይ 2850 ሜትር ከፍታ አለው፡፡

የአካባቢው የህዝብ ብዛትም ከሁለት መቶ ሺህ በላይ መሆኑ ተገልጿል፡፡

ህዝቡም ሚደማውን ሩዝ፣ ሊላውንም የቢራ ገብስ እየዘራ ይተዳደራል፡፡ ሸንኩርት፣ ቲማቲምና ሌሎች አትክልቶችንም ያመርታል፡፡

ርብ እና ሸኒ ከሚባሉ ወንዞች አሸዋ እያፈሰ በመሸጥ የሚተዳደረውም ብዙ ነው፡፡ የኖራ ድንጋይና እያሌ የከበሩ ድንጋዮችም በአካባቢው ይገኛሉ፡፡

ጥንታዊቷ የባሪያ ንግድ መናኸሪያ ከተማ ይፋግ ስክሪኑ ላይ መጣች፡፡ ግራምዳ ከሚባለው ጥንታዊ ዋርካ ስር ትልቅ ድንጋይ ተቀምጧል፤ የባሪያው ጉልበት የሚፈተንበት ግዙፍ ድንጋይ፡፡ ይህን ድንጋይ ተንገዳግዶ የተሸከመ ባሪያ በውድ ዋጋ ይሸጥ እንደነበር ተገልጾ ታለፈ፡፡

ቀጥሎ የቀሻ እንድሪያስ፣ የወይን ቀሻ፣ የጣራ ገዳም ተራሮች፣ በአጼ ቴዎድሮስ የተበረከተውና 15 ኪሎ ግራም የሚመዝነው የወርቅ ዘውድ የሚገኝበትና አንድ ሰው ሊሸከማቸው የማይችሉ ግዙፍ የብራና መፃሕፍት የሚገኙበት ሚካኤል ደብር፣ ጊዮርጊስ ወልደ አሚድ የሚባሉ ሰው ስለዓለም አጀማመርና አፈፃፀም በዝርዝር ፅፈው ያስቀመጡት መፅሐፍ የሚገኝበት ብርኩቱ ማርያም፣ ከአዲስ ዘመን ከተማ 35 ኪሎ ሜትር ያህል ርቀት ላይ የሚገኘውና ስድስት መቶ ሜትር ከፍታ ያለው የወህኒ አምባ ተራራ ምስል ሳይቀር በስክሪኑ ላይ መጥቶ ሄደ፡፡ የወህኒ አምባ ተራራ በጎንደር ነገስታት ዘመን ልዑላኑ ይጋዙበት የነበረ የግዞት ተራራ ነው፡፡ እንዱን እስር ሊላውን ለማንገስ ሴራ የሚሸረብበት ጥንታዊ እስር ቤት፡፡ በተራራው ውስጥ ስላሉ ምስጢራት ብዙ ያልተጠና ነገር ቢኖርም ኢትዮጵያውያን ይህንን ተራራ አይጎበኙትም፡፡ የውጭ ሀገር ጎብኚዎች ግን በተደጋጋሚ በሄሊኮፕተር ሲያርፉበት ታይቷል፡፡

እንጎታ ያለውን ጭንቀት ለማርገብም ይሁን አልያም ሆን ብላ ይሆን ባይታወቅም በአካባቢው የሚገኙ እፅዋትንና እፅዋቱትን ሁሉ ሳይቀር ትዘረዝር ጀመር፡፡

ከእፅዋት ዓይነቶች ጀመረች፡፡

ጨፌሮ፣ ቆጥቆጦ፣ ሽንበቆ፣ ቅሞ፣ መቅመቆ፣ ግመሮ፣ ትርንጎ፣ ጋቢሎ፣ ግራር፣ በለስ፣ እምብስ፣ አጣጥ፣ እንቦይ፣ እንኮይ፣ እንዶድ፣ ቅንጭብ፣ ቁልቋል፣ አጋም፣ አዛምር፣ ልንብጭ፣ እጣን፣ ጥንባጥንቢት፣ የንዶግ ሀረግ፣ ልንብጭ፣ ጎርጀጅት፣ ፍየለፈጅ፣ አስተናግር፣ ብሳና፣ ክትክታ፣ ሰሚዛ፣ ብሽብሽ፣ ሰርከበባ፣ ቀጋ፣ ቆጠጢና፣ ቀንጣፋ፣ ባንባ፣ ሾላ፣ ዋርካ፣ ቡና፣ ለንቋጣ፣ ዝግባ፣ ግራዋ፣ ናጫ፣ አሽ፣ ቀርከሀ፣ ቄንዶ በርበሬ፣ ኩሸሌ፣ ዳማከሴ፣ ሽንሽና፣ ብርብራ፣ ኮባ፣ ችብሀ፣ ወይራ፣ ቃጫና፣ ሙጃ፣ ጃካራንዳ፣ የጠጣቆስጥ፣ አጣጥ፣ ቀረጥ፣ ሎል፣ እሳት ላሽ፣ ጥቁር እንጨት፣ የክብሪት እንጨት፣ ግተም፣ ኮሶ፣ . . . እያለች የዛፍ ዓይነት ስትዘረዝር ከመሃል ሳቅ የሚያመልጠው እየበዛ መጣ፡፡

እርሷ ግን ጆሮ ዳባ ልበስ ብላ የወፍ ዓይነቶችን ሳይቀር መዘርዘር ጀመረች፡፡ ውጥረቱን እንዳረገበችውም ተገንዝባለች፡፡ ያሳቃቸው ይህን ሁሉ ዛፍ ብዙዎቹ አለማወቃቸው እንጂ የእርሷን መዘርዘር እንደሞኝነት ቆጥረውት እንዳልሆነም ተገንዝባለች፡፡
ሽግራ፣ ዋርዳ፣ ዋልያ፣ ሳቢሳ፣ ወረቤ፣ ቢጫወፍ፣ ድንቢጥ ወፍ፣ የመስቀል ወፍ፣ ዳክዬ፣ ቆቅ ጻልቃን፣ ጣልቃን፣ ግሪሳ፣ ሲሳ፣ ቁራ፣ ጥንባንሳ፣ ጨጩሌ፣ ጎመለል፣ ግንደ ቆርቁር፣ ሽመላ፣ ዋላ፣ እርኩም. . . ሳቁ እየበረከተ የቧን ድምፅ እየዋጠው ሲመጣ ዝርዝራዋን አቁማ አብራ ትስቅ ጀመር፡፡

"እንወቀው ለማለት ያህል ነው፡፡ አሰልቺ ይሆናል ብዬ ፈርቼ ነበር፡፡ እንዲህ የሚያስቅ መሆኑን ባውቅ ኖሮ ብዙ የምዘረዝረው ነበረኝ፡፡ እነዚህ ዛፎች እና አዕዋፋት በጊዜ ሂደት ልክ እንደኛ መጥፋታቸው አይቀርምና ቢያንስ ለትዝታ ስል ነው የዘረዘርኳቸው፡፡" ካለች በኋላ የስክሪኑ ምስል እየቀረበ እየቀረበ በትክክል እነሱ ያሉበትን አካባቢ እየለየ መጣ፡፡

ከታች ከአዲስ ዘመን ከተማ ደክቶ እነሱ እስካሉበት የተከበበ ተራራ ድረስ ያለውን ጓዳ ጎድጓዳ ታሳያቸው ጀመር፡፡ አዲስ ዘመን ከተማ እስከ ጭቃ ሰፈር፣ አበባዬ ጥቅጥቅ ደን፣ ቅድስት ሀና፣ ማረሚያ ቤቱ፣ ቢትወደድ ዋርካ፣ ፖሊስ ሰፈር፣ የውሃ ታንከር፣ አላቦ ሜዳ፣ ጌሾ ሰፈር፣ ሙቃራ ተራራ፣ ወደ እብናት

የሚወስደው መንገድ፣ የሊቦ ገመገም፣ የዙንዝ ሸለቆ፣ የኪብራ ወንዝ፣ የሸኒ ወንዝ፣ እስጢፋኖስ ቤተክርስቲያን፣ ደራጣ፣ ቅቤን ባህር፣ ዜና ማርያም፣ ሰበር ባህር፣ ማንቶግራ ሸለቆ፣ ምርጫ ደብር፣ ደቦች፣ አቢንጋ፣ ዳብራ፣ እምባ ተራራ፣ ኩሪት ዋሻ፣ ጻሞቶች መንደር፣ ቋላ ዮሐንስ፣ ከወረታ ወደ ጎንደር የሚወስደው መንገድ ወዘተረፈ. በስክሪን ላይ ሲተከሉ ሲንቀሉ ከቆዩ በኋላ አንድ የመሰበ ወርቅ ቅርፅ ያለው ተራራ መጥቶ ስክሪንን ሞላው፡፡ ይህ ተራራ እነሱ አሁን በክርሰ ምድሩ ውስጥ የሚኖሩበት ጣቅርን ተራራ ነው፡፡

የሚራኝ ዓይኖች ዕንባ አቀረሩ፡፡ በዚህ ተራራ ክርሰ ምድር ውስጥ የተረገዘው ሽል ሲጨነግፍ ምናልባት ቀናት አለበለዚያ ሰዓታት እንደቀሩት የሚያረዳ ሀሳብ በአእምሮው ውስጥ ተመላለሰ፡፡ ለሚራኝ ይህ ምስጢራዊ ተራራ ከእንግዲህ ምስጢር ሆኖ አይሰነብትም፡፡ የእንጎታ የአካባቢ ገለፃ ለመጨረሻው የሞት ሽረት ትግልና ከተራራው ከበባ ሰብሮ ለመውጣት ለሚደረገው ፍልሚያ ካርታ ለማዘጋጀት የሚያገለግል ገለፃ ነው፡፡ ከእንግዲህ ካርታውን ነድፎ ከበባውን ለመስበር መዘጋጀት የሚራኝና የመሰሎቹ ስራ መሆኑን አላጣውም፡፡ እንጎታ ገለፃዋን አጠናቃ በሞቀ ጭብባ ታጅባ ወደ ቦታዋ ተመልሳለች፡፡ ቀጣዩ የሚራኝ ገለፃ ደግሞ ከሻይ እረፍት በኋላ ይቀጥላል፡፡ ለሻይ ዕረፍት ሲወጡ ደግሞ በሚራኝ አእምሮ ውስጥ አንድ አስጨናቂ ሀሳብ መጣ፡፡ 'ምናልባት ለፍልሚያው በቂ ዝግጅት ሳናደርግ የከበበን ኃይል ተራራውን ሰብሮ ገብቶ እንደ ንፍሮ ይቀቅለን ይሆን?'

# ፳፬

ኪራክስ የአባቱን ማስታወሻ ሊያገባድድ ጥቂት ገፆች ሲቀሩት የደረሰበት ምስጢር እጁን አፉ ላይ አስጭኖታል፡፡ ከዚህ ሁሉ በኋላ የተገለጠለት ነገር ግልጽ በሚመስለው ዓለም ውስጥ እያሉ ድብቅ ጉዳዮች እንዳሉ ነው፡፡ ጋሙስ የተባለ ኃያል ህቡዕ ድርጅት ኢትዮጵያ ውስጥ ይኖራል ብሎ መቼም ቢሆን ገምቶ አያውቅም ነበር፡፡ ህቡዕ ድርጅት መኖሩ ሳይሆን ያስደነገጠው ድርጅቱ የተቋቋመበት ዓላማ ነው፡፡ የአባቱ ማስታወሻ ከድርጅቱ ስያሜና ትርጉም ጀምሮ ሁሉ ነገሩን ሆጭ አድርጎታል፡፡

ጋሙስ የሚለውን ቃል አለቃ ኪዳን ወልደ ክፍሌ የተባሉ ሊቅ "መጽሐፈ፡ ሰዋስው፡ ወግስ ወመዝገበ፡ ቃላት ሐዲስ" በሚባል መጽሐፋቸው ውስጥ እንዲህ ያስቀምጡታል፡፡ "ጋሙስ፤ የሱርት ቋንቋ ጋሙሽ ይበጥል፤ ጎሽ፡ ቀንደ ሹል፡ የበረሓ፡ እንስሳ፡ መልኩ የበሬ ጠባዩ ያውሬ፤ እንዳንበሳና፡ እንደ ነብር፡ ዓዳኝን የሚሻ፡ የሚከተል፡ በቀንዱና በግሩ የሚበቀል፡ ገብጦችና፡ ህዶች የሚያጠቡትና የሚጠምዱት ጠጉረ ሥሥ፡ ቀንደ ገባሳ፡ ሻኛ የሌለው፡ ገራም፡ ጭምት፡ የቤት ጎሽ ልባቸው፡፡" ሲሉ ይገልጹታል፡፡

በጠቅላላ ጋሙስ ማለት ጎሽ ማለት ነው፡፡ መልኩ የበሬ ጠባዩ ያውሬ፡፡ ጋሙስ የተባለውን ድርጅትና ጠባዩን በትክክል የሚገልፅ ስያሜ ነው፡፡ የኛው ጋሙስም መልኩን ከበሬ ጠባዩን ካውሬ በመውረሱ ከኢ በላይ ምስክር አያገኝም፡፡ ቅዳሙን ከበሬ ቀንዱን ከጎሽ የተዋስ በሰዎች የተቋቋመ ጠባዩ የአውሬ የሆነ ድርጅት ነው፡፡

ጎሽ በዱሯዋ እንደምትዋጋ እንዲሁም ጋሙስም ሳይቋቋመው ለካል ሟች ነው፡፡ ለአቅድሚ እንደገለፅኩት ይህ ድርጅት የተቋቋመው በዘጠኝ ሰዎች ነው፡፡ ያቋቋሙትም ከፍተኛ የገዥው ለካል ሰዎች ናቸው - በ1989 ዓ.ም፡፡ ጋሙስ የተቋቋመበት ዋና አላማ ባጭሩ የከፍተኛ ባለስልጣናትን ቀጣይ ስጋ ፋንታ ማመቻቸት ነው፡፡ ገዥው ፓርቲ ከተፈናጠጠበት የስልጣን ኮርቻ ላይ ምናልባት ቢወርድ ውስን የሆኑና ጋሙስን ያቋቋሙት ባለስልጣናት ያለአንዳች እንቅፋት

ተረድቷል፡፡ በሀሳቡ ወደ ተራራው እንደገባ አክሎማ ላይ ዘሎ ሲከመርበት እያናን እንቆ ትንፋሹ አጥሮት ሲሞት ታየው፡፡ ይሁን እንጂ ወደ ተራራው እንዲህ በቀላሉ መግባት እንደማይችል እንደገና ተገነዘበ፡፡ ተራራው ተከቧልና፡፡ እንደገና ሌላ ብኽርታ ሰውነቱን ሲወረው ተሰማው፡፡ አባቱ ቁልፉን ያስቀመጡት የት እንደሆነ አለማወቁን አስታወሰ፡፡

# ፳፫

የሚራሹ ንግግር "ትውልዱን ማዘጋጀት" የሚል ርዕስ እንዳለው ከገለፀ በኋላ ሰፊ ትንተናውን ቀጥሏል፡፡

"......... እንግዲህ ወደ ማይቀረው ፍልሚያ ተገደን መግባታችን ነው፡፡ ይህም ሲሆን ለምን እንደኖርን መታወቅ ያለበት ጉዳይ ነው፡፡ የእኛ አላማ ትውልዱን ማዘጋጀት እንደሆነ ሊታወቅ ይገባል፡፡ ኢትዮጵያ የተዘጋጀ ትውልድ ኖሯት አያውቅም፡፡ ስላለው ኑባሬ፣ ስላለው ሥርዓትና መሪ እንጂ በቀጣይ ምን ዓይነት ሥርዓት ምን ዓይነት መሪ ያስፈልጋል ብሎ የሚጠይቅና የሚዘጋጅ ትውልድ የላትም፡፡ ኢትዮጵያ የሚጋጅ መሪ እንጂ የሚዘጋጅ መሪ ኖሯት አያውቅም፡፡ ትውልዱ ለታናሽ ነገር ሳይሆን ለታላቅ ነገር ራሱን ማዘጋጀት አለበት፡፡ ትውልዱ የጋራ ራዕይ፣ የጋራ ህልም፣ የጋራ ትልም እንዲኖረው ነው አላማችን፡፡ ይህ አላማችን ሟች አለመሆኑን እኛም፣ ባላንጣዎቻችንም ማወቅ አለባቸው፡፡ እኛ የምንመኘው በተስፋ የተሞላ ብርሃናማ ትውልድን ነው፡፡

"ትውልድ በወል ተስፋ ሲቆርጥ ለአንድ ሀገር ከዚህ የከፋ ጉዳት የለም፡፡ ግለሰቦች እንደ ግለሰብ ተስፋ ይቆርጣሉ፡፡ ሙጣጭ ተስፋ ያጣ ግለሰብ ራሱን ያጠፋ ይሆናል፡፡ አንድ ሰው ጎደለ ብንል እንኳ ጉድለቱ እንደግለሰቡ አቅም ይታት በተቀበረው ዕውቀትና በህይወት ቢኖር በሚሰጠው ጠቀሜታ ተሰልቶ ሂሳብ ማወራረድ ይቻል ይሆናል፤ እንዳስፈላጊነቱም ይረሳል፡፡ ትውልድ በጋራ ተስፋ ሲቆርጥ ግን አንገቱን ለገመድ እጁን ለማንድ አይሰጥም፤ ውስጡ ሞቶ አዕምሮው ገምቶ ሲንገላጀጅ ይኖራል እንጂ፡፡ ህዝብ በጋራ ተስፋ ሲቆርጥ የአንድ ትውልድ ያህል ወደ ኋላ ይመለሳል፡፡ የሠራውን ያፈርሳል፡፡ የኋላ ታሪኩን ያወድማል፡፡ የወደፊቱን ያጨልማል፡፡ በሕዝብ

የሚያላምጠው አይጠፋም፡፡ ጊንጥ የሚናድፈው ካጣ ራሱን እንደሚነድፍ ሁሉ፣ አንዳንድ ሥርአተ መንግሥታት ሌላውን ነድፈው ሲገድሉ ማየት የተለመደ ነው፡፡ ችግራችን ራሳቸውን አሉዱ ስንል መኖራችን ነው፡፡ በዚህ መሀል ዘለአለም ሁኔታ መታሰብ አለበት፡፡ እንደ ድርጅት ዴርቶጋዳ የሀገሪቱ ቋሚ ያሳስበዋል፡፡ የሀገሪቷን ቋሚ ጉዳዮች ተሸክሞ የሚኖር ይህ ጉዳይ እንዲፈጠር ገና ገና ተግተን እንሠራለን፡፡ አራት ኪሎ ትውልድ ብዕር ይዞ በምርጫ ገብቶ በምርጫ ሲወጣ፣ ወረቀትና እየጠጣ በነፃነት የሚንቀሳቀስ ሰው በየካፌው ቡናውን እስኪኖር ተግተን እንሠራለን፡፡ ለዚህም የትኛውም ጦርነት አያፈራርሰንም፡፡ ትውልዱን በሞራልም፣ በመንፈስም፣ በአካልም እናዘጋጃለን፡፡ 'ተልባ ቢንጫጫ በአንድ ሙቀጫ' የሚሉትን ጫጫታችን ከተልባ ጫጫታነት ወደ መብረቅ ብልጭታነት የተለወጠለት የሙቀጫዎቹ፣ የአስወቃሪዎቹ እና የወቃሪዎቹ አወዳደቅ የከፋ ይሆናል፡፡ የዚች ሀገር ፈውሷ ራሱ በሽታዋ ነው፡፡ የቆምንለት ዓላማ ያልገባቸው ከበውናል፡፡ ያስከበቡን እንጂ የከበቡን ስለ እኛ የሚያውቁት ነገር የለም፡፡ አንድ የወንበዴ ቡድን ደምስሱ ተብለው ከበውናል፡፡ ጠላቶቻችን እውነቱን አይነግሯቸውም፡፡ ምክንያቱም፣ ማንነታችንን ከነገሯቸው አንድ ጥይት እንኳ አንተኩስም ሊሉ ይችላሉ፡፡ ከበባውን ወደ መስበር ስንገባም፣ የኖርንለት የምናኖረውና የምንኖርለት አላማ እንዳለን በማመን ነው፡፡ ይኸውም ትውልዱን ማዘጋጀት ነው...... አመሰግናለሁ፡፡" ሚራዥ ወረቀቶቹን ሸክፎ ከመድረክ ሲወርድ ሞቅ ያለ ጭብጨባ አጀበው፡፡

"ማነው የከበበን?" የሚለውን ንግግር የሚያቀርበው አያና ተፈሪ ሚራዥን ተክቶ መድረኩ ላይ ቆመ፡፡ ሚራዥ፣ ግንጊዳና ሳዶፍ 'ምን ይል ይሆን?' በሚል ከሌሎች በተለየ ተጠባበቁት፡፡

ለሁለት ቀናት ያህል ጌራ ከሱሉልታ ሳይወጣ ቆይቷል፡፡ ሜሮዳን የበላት ጅብም አልጮኸም ነበር፡፡

ዛሬ ከመሸ ግን የኮ/ል አሊጋዝ ሱሉልታ መድረስ አንድ ጭምጭምታ ይዞ ብቅ ብሏል፡፡ ይህውም ሜሮዳ ወደ አዲስ ዘመን እንደተወሰደች የሚገልጽ መረጃ ነበር፡፡

ለጌራ ግልፅ ያልሆነለት ነገር ሜሮዳን ወደ አዲስ ዘመን መውሰዳቸው ያለው ፋይዳ ነው፡፡ ኮ/ል አሊጋዝም በዚህ ጉዳይ ላይ ግልጽ የሆነ አስተያየት አልሰጡም፡፡ እንደ እርሳቸው አባባል ሜሮዳ ወደ አዲስ ዘመን የተወሰደችው ሌላ ከድርጅቱ ያላፈተለከ ምስጢር ካለ እሱን ለመመርመር ይሆናል የሚል ነው። ነገር ግን ጌራ ስለ ድርጅቱ ከዚህ በኋላ ያልታወቀ ነገር ያለ አልመሰለውም፡፡ ኮ/ል አሊጋዝ እንደለው የገለፁት፤ እስከ አሁን እነ ሚራዥ ከበባውን ለመስበር አለመሞከራቸው ግራ እንዳጋባቸው ነው፡፡ እንደ እርሳቸው ስጋት ከበባው ቶሎ ካልተሰበረ ሌላ ኃይል ተጓጉዞ ሊደርስ ስለሚችል የኃይል አለመመጣጠን ይከስታል የሚል ነው።

የኮ/ል አሊጋዝ አመጣጥ የሱሉልታውን ቡድን ወደ አዲስ ዘመን ለማንቀሳቀስ መሆኑ ታውቋል፡፡ በተራራውና ከተራራው ውጭ ያለው ግንኙነት በመቋረጡ በተራራው ውስጥ ያለውን ዝግጅት ባይረዱም፡፡ በውጭ ያለውን ኃይል በማሳሰብ የሞት ሽረቱን ትግል ከውጭ ሆኖ እንዲቀላቀል ለማድረግ ነው፡፡ አስቸጋሪ የሆነባቸው አስቀድሞ በተሰጠ ትዕዛዝ መሰረት አብዛኛው የዴርቶጋዳ አባል ስልኩን እንዲዘጋና ምንም አይነት መልዕክት ከማንም ጋር እንዳይለዋወጥ መደረጉ ነው፡፡ ሆኖም ቤቱን የሚያውቁትን በሩን እያንኳኩ መሰብሰብ የቻሉት ሃያ ሰው እንኳን አይሞላም፡፡

ኮ/ል አሊጋዝ የገበሬ ልብስ እያለበሱ ያገኙትን አዲስ ዘመን መሳክ ጀምረዋል፡፡ በዚህ ምክንያትም እግሬ ሁሉ ወደ የበለ ማንቀሳቀስ ከመጀመራቸው በፊት የሱሉልታውን የተላከው ኃይል እና እዚህ ያለው ወደ አዲስ ዘመን ሲገናኝ የሚተዋወቅበት አንድ የምስጢር ቃል በማለማመድ ላይ ናቸው፡፡

ከፊል የቄስ አለባበስ፣ ከፊሉ የሙስሊም አለባበስ፣ ከፊሉ የገበሬ አለባበስ እንዲለብስ ከተደረገ በኋላ ተራ የጉዞ ትኬቶችን እየገዛ ወደ ስሜን እንዲከት ተደረገ፡፡

ጌራ ግን የከተሜ ልብስ እንደለበሰ ከኮ/ሉ ጋር በግል መኪናቸው እንዲሳፈር ሆነ፡፡ ከሱሉልታ ተነስተው ዓባይ በረሀ እስኪደርሱ ድረስ በጌራና በኮ/ል አሊጋዝ መካከል አንዳችም የቃላት ልውውጥ አልተደረገም፡፡

"በምናችን እንፋለማለን?" ሲል ጠየቀ ጌራ፡፡ "ዱር33 እንደሆነች ተራራው ውስጥ ናት፡፡"

"ግዴለህም ... በድንጋይም ቢሆን እንፋለማለን፡፡ ዳዊት ጎልያድን በጠጠር እንደጣለው አታውቅም እንዴ?" ኮ/ሉ ፈገግ አሉ፡፡

"የምሬን እኮ ነው፡፡ ዱርፀዩን ብይዝ ኖሮማ ማን ይቀምሰን ነበር! ምን ያረጋል እድል ከኛ ጋር አይደለችም፡፡ ሁሉ ነገር አስቀድሞ ተበላሽቷል፡፡ ሆን ተብሎ የተሸረበ ሴራ ሳይኖር አይቀርም፡፡"

"ማንን መጠርጠር ይቻላል?"

"እሱማ አስቸጋሪ ነው፡፡"

ለሊቱ በጉዞ ተጋመሰ፡፡ ባህር ዳር ሲደርሱ እየነጋ ነበር፡፡ ጌራ ወደ ጎንደር በሚጓዝ አውቶብስ እንዲሳፈር ተደረገ፡፡ ኮ/ሉም በቅፅበት መኪናቸውን አስነስተው ከአካባቢው ተሰወሩ፡፡

# ፳፺

አያና፣ የከበባቸው ኃይል ማን ሊሆን እንደሚችል ግምት የሚያስቀምጠውን ንግግሩን በማስማት ላይ ነው። የመረጃ አቀራረቡ ከጠቅላላው ጉዳይ ወደ ዝርዝር ጉዳዮች የገባ ይሁን እንጂ ብዙዎችን ያስለቸና የተንዛዛ ነበር። በቀጥታ ግምቱን ከማስቀመጥ ይልቅ አጠቃላይ የኢትዮጵያን ወታደራዊ አሰፋፈር ከሰሜን እስከ ደቡብ፣ ከምስራቅ እስከ ምዕራብ ይተነትን ጀመር። ከምስራቅ መጀመሩ ሁሉንም ግራ አጋብቷል።

"የኢትዮጵያ ወታደራዊ አሰፋፈር በጥቅሉ የሚከተለውን ይመስላል።" ሲል ነገሩን መቦርቀቅ ጀመረ።

"በምስራቅ ምስራቅ እዝ ይገኛል። የማዘዣ ጣቢያው ሀረር ሆና ከድሬዳዋ እንስቶ ኦጋዴንንና የሶማሌ ክልልን አካሎ እስከ ኢትዮጵያ- ሶማሊያ ድንበር ያለው የእዝ ቀጠናው ነው። በውስጡም የሚከተሉትን ክፍለ ጦሮች እና ሌሎችን ይይዛል። 12ኛ ክፍለ ጦር (መተማ)፣ 13ኛ ክፍለ ጦር (በላይ ዘለቀ)፣ 1ኛ ሜካናይዝድ ብረት ለበስ ክፍለ ጦር..... በጉራላ ውጊያ የተስላቸ ይሁን እንጂ እንደኛ ካለ ሽማቂ ቡድን ጋር የመዋጋት ልምድ ያለው ነው።" አያና ይህን ሲል ሚራኘ በደም ፍላት አቋረጠው።

"ይቅርታ! አያና!..... እኛን ሽማቂ ቡድን ብለህ የጠራህበት ምክንያት አልገባኝም።" ሲል አስተሀቀረው።

"ይቅርታ። ይህ ስህተት የተፈጠረው በቋንቋ ችግር እንደሆነ ይታወቅልኝ።" ሲል አያና ነገሩን አላዝቦት አለፈ። "ከምስራቅ ወደ ደቡብ ስንሻገር፣ ዋና ማዘዣውን በሀዋሳና በሻሸመኔ መካከል ከዋናው መንገድ 1.5 ኪሎ ሜትር ገባ ብሎ በሚገኝና፣ ልዩ ስሙ ቶጋ በሚባል ብካምፕ ያደረገውን አግአዚ ልዩ ኮማንዶ ክፍለ ጦርን እናገኛለን። ክፍለ ጦሩ በስዎቹ ብቻ የሚታዘዝ በመሆኑ ወደየትኛውም አቅጣጫ ሊላክ ይችላል። አስፈላጊ ሆኖ ከተገኘ እሱንም ሊልኩብን ይችላሉ።" አያና ይህን ብሎ ንባቡን አቆመና ባይኑ ሁሉንም ቃኘ።

"አሰፋፈራን እኮ አላልንህም አያና?" አለው ሳዶፍ ዓይን ላይን እንደተጋጨ።

ጦር(ዳሉል)፣ 43ኛ ክፍለ ጦር(ቅዕል ስሙን ረስቼዋለሁ) እና እዚህ ከቅርባችን አዘዞ ሎዛ ማርያም ስር የሚገኘው አምስተኛ ሜካናይዝድ ክፍለ ጦር በውስጡ ያሉ ክፍለ ጦሮች ናቸው፡፡ ካሉት ሌሎች ዕዞች ይህኛው ቀለል ያለ ይመስለኛል፡፡ ሶስት ክፍለ ጦሮች ብቻ ያሉት ከመሆኑም በተጨማሪ በእህል አጨዳና በቦቅሎ ሽልቀቃ የተሰላቸ ነው፡፡"

"ጦርነት የናፈቀው ጦር እንዳለ መናገርህ ይሆን?"

"ይቅርታ እያና! እባክህን ይህን መሰል ቀልድህን አቁም፡" ሚራዥ እጁን አወናጨፈ፡፡

"ጨርሻለሁ፤ ... አመሰግናለሁ፡፡" እያና ወረቀቶቹን ሸካክፎ ከመድረኩ ወረደ፡፡

"ከዚህ ሁሉ መረጃ ውስጥ ሊገባኝ የቻለው የሀገሪቱ የኃይል አሰላለፍ እንዴት ሚዛኑን የሳተ እንደሆነ ብቻ ነው፡፡" አለ ሚራዥ እያና እየተቀመጠ እያለ፡፡ "የረሳኸው ነገር ግን አለ፡፡ እዚህ ዘጠኝ ኪሎ ሜትር ያህል ርቀት ላይ ቀድሞ ሰፍሮ የነበረውን አንድ ሬጅመንት እና ይፋግ ላይ የነበረውን አንድ መድፈኛ ብርጌድ ረስተሃል፡፡ አሁን ይኑሩ አይኑሩ አላውቅም፡፡ የሆነው ሆኖ በመጀመሪያ ሊልኩብን የሚችሉት ቃኚ ሻለቃ መሆን አለበት፡፡ አሁን የቃኚ ሻምበል መሰለኝ የሚሉት-ካልተሳሳትኩ፡፡ ቃኚ ሻለቃ የእዙ መረጃ ነው፡፡ ተግባሩ ተዋጊ እህዱን ከመጠበቅ በተጨማሪ በጦርነት ወቅት ቀድሞ በመተንኮስ ጠላት ተኩስ እንዲከፍት አድርጎ የያዘውን መሳሪያ ማጥናት ነው፡፡ የቃኚ ሻምበል ይህን ዓይነቱን ተግባር ሳያከናውን ወደ ጦርነት አይገባም፡፡ ይህ መደበኛ ግዳጅ ነው፡፡ ጠላትን በመተንኮስ፣ የጠላት አቀማመጥን፣ አሰላለፍን እና አቅምን በማጥናት ለአመራሮች ሪፖርት የሚያደርገው ይኸው ቃኚ ሻምበል ነው፡፡ ለመሀንዲሶች (ፈንጂ አፅጂዎች) ሽፋን መስጠት፣ ከኋላው ለሚገባው እግረኛ ተዋጊ (ለዋናው ተዋጊ) መንገድ መጥረግ ነው ሥራው፡፡ የሰው ኃይሉም ከመቶ አይበልጥም፡፡ ትጥቁም ቢሆን ይህን ያህል የተጋነነ አይደለም፡፡ የነፍስ ወከፍ መሳሪያ (ክላሽ)፣ ከስምንት ያልበለጠ ስናይፐር፣ ከሶስት እስከ አራት መትረዬስ፣ ከአራት ያልበለጠ ላውንቸር እና ከዲሽቃ በላይ አይታጠቅም፡፡ እያና ያቀረብከው መረጃ ተስፋ በመቁረጥ እጃችንን እንድንሰጥ ፍርሃት የሚለቅ ከመሆን ያለፈ ሌላ ፋይዳ ያለው አልመሰለኝም፡፡"

"ይቅርታ ወንድም ሚራዥ እኔም እንዳንተ የድርጅቱ አባል ነኝ። እኔም እንዳንተ ለድርጅቱ ብሰጥ የማትበቃኝ እንዲት ነፍስ ነው ያለችኝ። እኔና አንተ ለድርጅቱ ልጅና የእንጀራ ልጅ የሚያደርገን ጉዳይ ያለ አይመስለኝም።"ሲል እያና የመልስ ምቱን ወነጨፈ። "እንደማገኛውም ሰው እንደራደር የሚል እቋም እንወጣርቅ ነበር። ያ የግሌ አቋም ነበር። አሁን ግን የድርጅቱን አቋም የመያዝ ግዴታ አለብኝ፤ ይገባሃሁም። እፍ አላፊ ባንነጋገር መልካም ነው።" ብሎ ዝም አለ። ሚራዥም እያናን ለማበሳጨት የሞከረው ሆን ብሎ ነበር። በብስጭት አንድ ነገር ካመለጠው ለመቅለብ። ሆኖም የእያና ስሜት እንዲህ በቀላሉ ሊፈታም ሆነ ሊደረስበት አልቻለም። ስብሰባውም ግቡን ሳይመታ ተጠናቀቀ።

# ፳፫

ኪራኮስ ቁልፉን ፍለጋ ሲዳክር ዋለ። ያልከፈተው ሳጥን ያልገለጠው መፅሐፍ አልነበረም። እንደገና በመመርመር አንዲት ፍንጭ ባያገኝ ኖሮ ተስፋ ወደመቁረጡ ተቃርቦ ነበር።

ሊሊያ መኪናዋን ከአፓርታማዋ መኪና ማቆሚያ እንዳቆመች ሽቅብ ወደ ቤትዋ ተመለከተች። በቅርቡ ተከራይቶ የገባው ሰውዬ መስኮት በጥቂቱ ገርበብ ብሎ አየች። ኪራኮስን በማጥመድ ላይ እንደሆነ የጠረጠረችው የዚህ ሰው መስኮት ከራሷ ክፍል አንድ ክፍል ዘሎ የሚገኝ ከመሆኑም ባሻገር ከኪራኮስ መስኮት ትይዩ ነበር። ይህ ሰው ሆን ብሎ ያን ክፍል እንደተከራየ ተጠራጠረች። ምናልባት ኪራኮስን ኢላማ ውስጥ ለማስገባት አመቺ ስለሆነ ይሆናል ስትልም ገመተች።

ገርበብ ባለው መስኮት አንድ ሹል ነገር ዘልቆ ያየች መሰላት- ጥቁር ሹል። የስናይፐር አፈሙዝ ይሆናል የሚል ጥርጣሬ አደረባት። አዕምሮዋን መናፍስት የወረሩት መሰላት።

19ኛው ገፅ በቀይ መከበቡ፣ 9ነኛው አንቀፅ በቀይ መጻፉ እና 7ተኛው አንቀጽ ከስሩ መሰመሩ ነበር ለኪራኮስ ፍንጭ የሆነው።

'አስራ ዘጠነኛው ገፅ፣ ዘጠነኛው አንቀፅ፣ ሰባተኛው መስመር!' ሲል ለራሱ አነበነበ። በመጻህፍት መደርደሪያው ዙሪያ እየተንጎራደደ ይህንኑ ነገር ያነበንብ ጀመር።

'አስራ ዘጠነኛው ገፅ፣ ዘጠነኛው አንቀፅ፣ ሰባተኛው መስመር!'

'አስራ ዘጠኝ'

'ዘጠኝ'
'ሰባት'
'አስራ ዘጠኝ፣ ዘጠኝ፣ ሰባት'
'አስር፣ ዘጠኝ፣ዘጠኝ፣ ሰባት'
ቁጥሮቹን በብጣቂ ወረቀት ላይ ፃፋቸው፡፡
'19፣9፣7'
'1997'
'አስራ ዘጠኝ ዘጠና ሰባት'

✻ ✻ ✻

ሊሊያ ደንዝዛ መኪናዋ ውስጥ እንደተቀመጠች ናት፡፡ ሰውዬው አልሞ ተኳሽ መሆኑን አልተጠራጠረችም፡፡ በመስኮቱ የዘለቀው ጥቁር ጫፍም የስናይፐሩ አፈሙዝ ለመሆኑ ጥርጥር የላትም፡፡ ኪራኮስ በመስኮቱ ብቅ ካለ ከዚህ አፈ ሙዝ የተላከ እሳት ግንባሩን እንደሚበረቅሰው አረጋገጠች፡፡ ከመኪናዋ በግድ እየተንቀጠቀጠች ወረደች፡፡

✻ ✻ ✻

"1997"

ምንም ትርጉም ሊሰጠው አልቻለም፡፡ ሌላ ገፆችን ሲያገላብጥ ቢቆይም ምንም ዓይነት ሌላ ፍንጭ ሊያገኝ አልቻለም፡፡ ምስጢሩ እዚሁ 1997 ውስጥ መኖሩን ተጠራጠረ፡፡ ቁጥሮቹን በአቀማመጣቸው መሰረት አባዛቸው- 567፡፡ እንደገና ደመራቸው- 26፡፡ ይህን ሁሉ አድርጎም ሊያገኝ የቻለው ምስጢር አልነበረም፡፡

ማስታወሻውን ገጥሞ ጥቂት ካሰበ በኋላ ወደ መስኮቱ መራመድ ጀመረ፡፡ ምናልባት ሊሊያን ለመጨረሻ ጊዜ ያይ እንደሆነ በማሰብ፡፡

✻ ✻ ✻

ሊሊያ ከመኪናዋ ከወረደች በኋላ ኪራኮስ የሚኖርበትን አፓርታማ መውጣት ጀምራለች፡፡ እግሯ እንክት እንክት ይልባት ጀመር፡፡

✻ ✻ ✻

ኪራኮስ ወደ መስኮቱ እየተራመደ እያለ በማስታወሻው የሽፋን ገበታ ላይ 1997 የሚለው ቁጥር ደብዘዝ ብሎ መፃፉን ልብ አለ፡፡ ቁጥሩ የተፃፈው በተለጣፊ ጠንካራ ነገር ላይ እንደሆነም አስተዋለ፡፡ ቀስ አድርጎ ላጠው፡፡ በውስጡ በ "ቶ" ቅርፅ የተሠራ ቁልፍ ተቀምጦ ነበር፡፡ በስስት ከመዘዘው ጭምቅ አድርጎ ወደ ደረቱ አስጠጋው፡፡

ወደ ኢትዮጵያ በመብረር ተራራውን ከውድመት የሚታደግበት ቁልፍ እጁ ላይ እንደገባ ካረጋገጠ በኋላ አንድ ስጋት አደረበት፡፡ እሱም ወደ ተራራው ሲደርስ ሁሉ ነገር ተጠናቆ እንዳይጠብቀው ነው፡፡ የአውሮፕላን ትኬት የሚቆርጥበት ደቂቃ ረዘመበት፡፡ ሆኖም ሊሊያን ሳይሰናበታት መሄድ እንደማይችል ልቡ ከነገረው በኋላ ወደ መስኮቱ የጀመረውን ርምጃውን ቀጠለ፡፡ ነገር ግን በሩ በቅፅበት ተበርግዶ ሊሊያ ተወርውራ ገባች፡፡ መናገር አልቻለችም፤ አፏ ተሳሰረ፡፡ የደረሰችበት ወደ መስኮቱ ለመጠጋት ሶስት ርምጃ ያህል ሲቀረው ነበር፡፡ ተወርውራ ተከመረችበት፡፡ የመነጋገሪያ ጊዜ አልነበራትም፡፡ እሱን ጥላ ወደኋላ ለመመለስ ስትቆም መስኮቱ ጥግ መሆንዋን አልተገነዘበችም ነበር፡፡ ኪራኮስ ለመነሳት ሲፍገመገም ከሊሊያ ደረት ደም ሲረጭ ተመለከተ፡፡ ተዝለፍልፋ ላዩ ላይ ወደቀችበት፡፡

# ፷፱

## አዲስ ዘመን + ጣቅርን ተራራ

ለሚራኘ አንድ መርዶ ተነገረው፡፡ በተራራው ውስጥ የሚላስ የሚቀመስ እንዳለቀ ያረዳው የምግብ ክፍል ኃላፊው "ለዛሬ ራት የሚበቃ ነገር እንኳን የለንም፡፡" ሲል ነበር አቀርቅሮ የነገረው፡፡

"ያለውን ሁሉ አሟጠህ ለዛሬ ራት ቆንጆ አድርገህ አዘጋጀው፡፡" ሚራኘ ትክሻውን ቸብ ቸብ አደረገው፡፡

"ት...ት... ትንሽ ትንሽ እየቀመስን ነፍስ መያዣ ብናስቀምጥ አይሻልም?"

"ጦርነቱ ሊጀመር ትንሽ ሰዓታት ብቻ ነው የቀሩት፡፡ ሁሉም ዝግጅት ተጠናቋል፡፡ ከበባውን ሰብረን የምንወጣበት ጊዜ እየተቃረበ ነው፡፡"

"አይመስለኝም ሚራኘ . . . ." አለ የምግብ ክፍል ኃላፊው ስጋቱ በግልፅ እየታየበት፡፡ " እነሱ እኮ እድሜ ልካቸውን ከጦርነት ጋር ያደጉ ናቸው፡፡ የሚሆን አይመስለኝም፡፡ በኛ በኩል በምርምር የደከመ ሳይንቲስት እና ከብዕር በቀር ብረት ጨብጦ የማያውቅ ኃይል ነው ያለን፡፡ እኔም ብሆን ከመክተፊያ በቀር የጠብመንጃ ምላጭ እንኳ ነክቼ አላውቅም፡፡"

"አትፍራ፡፡ ፍርሃት ጥሩ ነገር አይደለም፡፡ ሁሉም ሽንፈት የሚመነጨው ከፍርሃት ውስጥ ነው፡፡"

ሚራኘ የምግብ ክፍሉን ለቆ ወደ ስልጠና ክፍሉ ነበር ያመራው፡፡ እንደተለመደው የፍልሚያ ዝግጅቱ እንደተጧጧፈ ነበር፡፡

በስልጠና ክፍሉ ውስጥ ዣንጊዳና ሳዶፍ የማሰልጠን ተግባሩን ተያይዘውታል፡፡ ለሰልጣኞች የአካል ብቃት፣ የመሳሪያ አጠቃቀም፣ በመሳሪያ እምነት ስለማሳደር፣ ስለ ዓላማ ፅናትና ስለ መንፈስ ጥንካሬ፣ ስለተቀናጀ እንቅስቃሴ፣ በእዝ ሰንሰለት ብቻ ስለመንቀሳቀስ፣ ስለማጥቃትና ስለማፈግፈግ ስልትና ጥቅም፣

ውጊያ የቡድን ስራ እንጂ የተናጠል ተግባር ስላለመሆኑ፣ ስለ ትግል ቋንቋ.... ወዘተርፈ በማስተማር ላይ ናቸው፡፡

ሲጻራ ሽኗ እየገፉ ቢሆንም ከስልጠናው ቦታ አልቀረችም፡፡ አንዳንድ የጦርነት ታሪኮችን ለሰልጣኞች በመተረክ የጦርነት ውጤቶችን መሠረት በማድረግ፣ ተሸናፊ ምን ስህተት ሠርቶ እንደተሸነፈ፣ አሸናፊው ምን ተግባር ፈጽሞ እንዳሸነፈ ስትተርክላቸው ነበር፡፡ ችግርን ስለመቋቋምና ስለጥብቅ ሥነስርዓት ጠቃሚነትም እንዲሁ፡፡

ሚራዥ ወደ ስልጠናው ቦታ ገብቶ ያለውን ጉድጉድ ከተመለከተ በኋላ በስፍራው የተገኙትን ሰዎች ያጤን ጀመር፡፡ ሻጊዝ የስልጠናው ተሳታፊ እሆናለሁ በማለት አሻፈረኝ በማለቱ፣ አብሮ እየሰለጠነ ነው፡፡

"እንዳንተ ሁሉን ለማወቅ የሚተጋ ሰው አይቼ አላውቅም!" ሲል ነበር ሚራዥ ወደሚሰለጥንበት ቦታ ሄዶ መደበቅ ያልቻለውን አድናቆቱን የገለጠለት፡፡ ሻጊዝ ፈገግ ብሎ ስራውን ቀጠለ፡፡ በላብ ተዘፍቋል፡፡ የውስጥ ልብሱ በላብ ከደረቱ ጋር ተጣብቋል፡፡

ሚራዥ ሌሎች ሰልጣኞችንም እየዞረ ተመለከተ፡፡ ሁሉም ስልጠናውን በትጋት ተያይዞታል፡፡ ማርዬ ዋቆ ማርዬ ከበድ ያለ የአካል ብቃት እንቅስቃሴ በመስራት ላይ ነበር፡፡ በአይን እንደተገጣጠሙ ፈገግ ተባባሉ፡፡ ከጥጉ አድያም የሚባለውና በመነፅሩ ታሪክ የሚታወቀው ጎረምሳ ደፋ ቀና ይላል፡፡ ሚራዥ ወደ አድያም ሄደ፡፡

"እህ ! እንዴት ነው እባክህ?!"

"ተያይዘነዋል!. . . ለክፉ አንሰጥም፡፡" ጫን ጫን ይተነፍሳል፡፡

"ጎበዝ ልጅ!. . ."

በተራራው ውስጥ የሚገኙት ሰዎች ብዛት ከሁለት ሺህ ስምንት መቶ በላይ ቢሆኑም ለፍልሚያው ብቃት እንዳላቸው ታምኖባቸው በመሰልጠን ላይ የሚገኙት ግን አንድ ሺህ አይሞሉም፡፡

ቀሪዎቹ ሽማግሌዎችና ሕፃናት ናቸው፡፡ ህጻናቱ ከዘጠኝ ዓመት እስከ አስራ ሰባት ዓመት ዕድሜ ያላቸው ሆነው የነገይቱን ኢትዮጵያ በደንብ ይረከቧት ዘንድ ከፍተኛ የሆነ ትምህርትና ፍቱን የሆነ ተግባራዊ ክህሎት የሚሰጣቸው ናቸው፡፡ በሳይንስ እውቀታቸው አስደናቂ ውጤት ያስመዘገቡትን እነዚህን ህፃናት ሚራዥ እንደዓይኑ ብሌን በመንከባከቡ ረገድ ወደር አልተገኘለትም፡፡ ከዚህ በተረፈ አንዳንድ በአካል ብቃታቸው ደከም ያሉት ሳይንቲስቶች በፍልሚያው እንዳይሳተፉ ተደርጓል፡፡

የሰዓቱ የአካል ብቃትና የመሳሪያ አጠቃቀም ስልጠና ከተጠናቀቀ በኋላ ሚራዥ ስለፍልሚያው አንዳንድ ገለፃዎችን ለማድረግ ወደ መድረኩ ወጣ፡፡

"…..ምናልባት ጦርነቱ በጨለማ የሚጀምር ከሆነ….." ሲል ንግግሩን ጀመረ፡፡ ሁሉም ከመድረኩ ስር ቆሞ ንግግሩን ያዳምጥ ጀመር፡፡ በአካል ብቃቱ ስልጠና የደከመ ሁሉ ከማለክለኩ በቀር ፀጥታ ሰፍኗል፡፡ "….የጨለማ ጦርነት እጅግ ከፍተኛ የሆነ ጥንቃቄን ይጠይቃል፡፡ የብርሃን ስህተት ከሠራህ ልትመታ ትችላለህ፡፡ ሲጋራ ማጨስ እና ተንቀሳቃሽ ስልክ ማብራት የከፋ አደጋ ያስከትልብሃል፡፡ ምሽግ ውስጥ ካልሆንክ በቀር ጥይቶችን ስትተኩስ ቦታ መቀያየር አለብህ! ቦታ እየቀያየርክ ካልተኮስክ የጥይቶችህ ብልጭታ በጠላት ኢላማ ውስጥ ያስገባሃል፡፡ በጨለማ ጦርነት ወቅት የእግርህ ኮቴ ጠላትህ ሊሆን ስለሚችል በጥንቃቄ መራመድ አለብህ፡፡ የውሃ ኮዳህ ሙሉ ካልሆነ ተንቦጫብሮ ሊያንቦጨቡጭህ ይችላል፡፡ የትጥቅ እንግብህ እንዳይንቀጫቀጭ ትጥቅህ የጠበቀ መሆኑን በቅድሚያ ማረጋገጥ ያስፈልጋል፡፡ ሌላው ቀርቶ የሚንቀሳቀስ ጥርስ ካለህ……." ሲል አዳራሹ በሳቅ ተናጋ፡፡ የሚንቀሳቀስ ጥርስ የሚለው እንዳሳቀቻቸው ስለገባው ሳቃቸውን እስኪገቱ ጠበቃቸው ሚራዥ፡፡

"እውነቴን ነው፡፡ የጨለማ ጦርነት ከፍተኛ ጥንቃቄን ይጠይቃል፡፡ ይህን በአፅንኦት ለመናገር ስል ነው፡፡ በሌላ በኩል ሰብሮ የመውጣት ውጊያም ጥንቃቄ የተሞላበት ውጊያ ካልተደረገ በቀር አዳጋች መሆኑን ለማስረዳት እፈልጋለሁ፡፡

ከበባን ለመስበር ውጊያው እንዳስፈላጊነቱ ማጥቃትንና መከላከልን አፈራርቆ መጠቀምን ይሻል፡፡ እኛ የምንጀምረው ከመከላከል ነው፡፡ በመከላከል ውጊያ ጊዜ መሬት ይዘን ስለምንከላከል እንደ የማጥቃት ውጊያ ከባድ አይደለም፡፡ መሬት ይዞ መዋጋት ከፍተኛ ጥቅም አለው፡፡መሬት፣ ለወታደር በአግባቡ ከተጠቀመባት እናቱ ናት፤ ካባከናትም መቃብሩ፡፡ እኛ ምሽግ ከያዝን እነሱ ተንሳፈዋል ማለት ነው፡፡ ስለዚህ በእነሱ ሰውነት ላይ የእኛ ጥይት ሲያርፍ የእነሱ ጥይት ግን በእኛ ምሽግ ላይ ነው የሚያርፈው፡፡ ስናጠቃ ግን የተገላቢጦሽ ነው የሚሆነው፡፡ እነሱ መሬት ይይዛሉ እኛ ደግሞ አየር ላይ ነን ማለት ነው፡፡ ስለዚህ የማጥቃት ውጊያችን እንደመብረቅ ብልጭታ ፈጣን መሆን አለበት ማለት ነው፡፡ ይሄው ነው!.....አሁን ገላችንን ታጥበን ወደራት ገበታ እንቀርባለን........በጣም ጥሩ፡፡ ሁሉም ወደ መለቃለቂያ ክፍሉ ከተተ፡፡

ከደቂቃዎች በኋላ በእራት ገበታው ላይ ሁሉም እጁን ታጥቦ ቀረበ፡፡

"ይህ የመጨረሻው ራት ነው ጓዶች!" ሲል መጋቢው ተናገረ፡፡

ሚራዥ መጋቢውን ጎተት አድርጎ ወደ ውስጥ ወሰደውና "ስማ! ከፍተኛ ምስጢር እኮ ነው ያባከንከው ገብቶሃል!?" እዚህ ውስጥ ለጠላቶቻችን መረጃ የሚያቀብሉ ሊኖሩ እንደሚችሉ መገመት አቃተህ?" ሲል ገሰፀው፡፡

"በል ወደ እራት መመገቢያው ግባና አባባልህን አስተባብል፡፡ 'ብሉ! ይጨመራል! እስክትጠግቡ ብሉ' እያልክ ተናገር፡፡"

"ጨምር ካሉኝስ?"

"ያልሰማህ መሰለህ ዞር ማለት ነዋ በቃ !"

"ሚራዥ ይልቁንስ አንተ ራትህን ብትበላ ይሻልሃል፡፡ ካለቀ በኋላ ከባዶ ሳህን ጋር እንዳትፋጠጥ፡፡"

"ግዴለህም የእኔን ላነሳው ጨምረህ ስጥ!"

"አብደሃል?... ወደ ጦርነት እኮ ነው የምትሄደው ወደ ሰርግ መሰለህ እንዴ?"

"የምልህን ስማኝ የእኔን ፋንታ ላነሰው አይተህ ጨምር፡፡ ለሲጻራ ያቀረብክላት ለሁለታችን ይበቃል፡፡ ወደ እርሷ ሳህን እጄን እሰዳለሁ፡፡"

"የነፍሰ ጡሯን?"

"ግዴለህም.... ነፍሰ ጡሮች የምግብ ፍላጎታቸው እንደሚቀንስ አታውቅም እንዴ?"

"ሚራዥ..... እኔ እኮ እርጉዝ አይቼ አላውቅም፡፡ ከልጅነቴ ጀምሬ እዚህ ተራራ ውስጥ ነው ያደኩ፡፡ ብርቅ ሆናብኝ ሆድ ሆዷን ስመለከት እውላለሁ፡፡ በናትህ ተንከባከባት፡፡ ታሳዝናለች፡፡ ሳያት ሆዴ ይንቦጫቦጫል... "

ሚራዥ በአባባሉ ፈገግ ብሎ መጋቢውን በቆመበት ጥሎት ወደ እራት መመገቢያው ክፍል ሂዶ ከሲጻራ ጎን ተቀመጠ፡፡ ሰሀኗ ባዶ ነበር፡፡

"ጠገብሽ?" አላት ባዶውን ሰሀን እያየ፡፡

"አልበላልሽ ሲለኝ ለሌሎች አከፋፈልኩት፡፡ አንተስ ጠገብክ?"

"አዎ ጠግቤያለሁ፡፡" አላት ሚራዥ ሆድ ሆዷን እየተመለከተ፡፡ "ዛሬ ደግሞ እንዴት ነው ጨመረ ልበል?"

"በጦርነቱ መሀል ጉድ እንዳያረገኝ ነው የፈራሁት፡፡"

"እዚሁ ትቆያለሽ፡፡"

"ምን ማለትህ ነው? ማን እንደሆንኩ የዘነጋህ መሰለኝ፡፡ ቢያንስ አንድ ቦታ ላይ የመትረየስ ተኳሽነቱን ሚና መወጣት አያቅተኝም፡፡"

"ይህ አጉል ጀብደኝነት ነው፡፡"

"ጀብደኝነት? እንደዛ አልከው?.... እዚህ ተቀምጬ እንደሴት የጦርነቱን ውጤት የምጠባበቅ ይመስልሀል እንዴ?"

"እንደ ሴት?" ሚራዥ ፈገግ አለ፡፡

"አላሰልፍሽም ማለት ትችላለህ፡፡ አዝናለሁ፡፡ አንተ ተው እንደዚህ መጥፎ አለቃ አትሁን፡፡"

"መጥፎ አለቃ?"

"አለቃ ጨምላቃ!"

"አለቃ ጨምላቃ አለሽኝ?. . . ካልሽ በኋላ ጉድ እንዳታረጊኝ እንጂ በተራራው በስተግራ ያለውን የመትረዬስ ምሽግ ትገቢበታለሽ፡፡"

በዚህ መሀል ማርዬ ዋቆ ማርዬ ወንዳልቆን እስከ መሰንቆው እየጎተተ ይዞት መጣ፡፡

"አንተ ሰነፍ አዝማሪ ሽልል እንጂ! አነቃቃ እንጂ! . . . መሰንቆህን እኮ ሸረሪት ዘጋበት!. . . ለመቼ ነው ያስቀመጥከው?. . . በፍልሚያ ወቅት ቱዘማ አያስፈልግም!. . . ዘራፍ ማለት ነው እንጂ!. . . ዘራፍ እኮ ትልቅ የስነልቡና ጥበብ ነው፡፡ ያገራችን ጀግኖች ያን ሁሉ ጦርነት ያሸነፉት በመሳሪያ ብዛት መሰለህ እንዴ? ዘራፍ በሚለው ቃል እኮ ነው፡፡ ዘራፍ በል እንጂ ጃል!... ጃሎ በል እንጂ ጃል?"

"ካልክስ መሰንቆዬ ናፍቃኝ ነበር!" ወንዳልቆ እየተንጎራደደ ያሸሞነሙነው ጀመር፡፡

"...ትመር እንደሆነ
ምረር እንደ ቅል፣
አልመር ብሎ ነው
ዱባ ሚቀቀል!..."

ሻጊዝ ሚራኘ ወዳለበት መጥቶ ወደ ውጭ ይዞት ከወጣ በኋላ "ምሽግ ምሽግ ትላለህሳ?! መቼ የቆፈርነው ምሽግ አለና ነው? " ሲል አፋጠጠው፡፡

ሚራኘ እጆቹን ዘርግቶ መዳፎቹን አሳየው መጅ አበጅተዋል፡፡ ጣቶቹም ቆሳስለዋል፡፡

"ምን ሆነህ ነው?" ሻጊዝ ዓይኖቹን እጆቹ ላይ ሳይነቅል ጠየቀው፡፡

"ከተከበብንበት ቀን ጀምረን ምሽግ እንቆፍር ነበር፡፡ በምስጢር እንዲያዝ ስለፈለኩ ግን ነው ይህን ያልገለፅነው፡፡ በተራራው ወገብ እንደመቀነት የዞሩ ሁለት ምሽጎች ተቆፍረዋል፡፡ የላይኛው ትክክለኛው ምሽጋችን ነው፡፡" ካለው በኋላ "ስንት እሳት የላሰ ጀግና እንዳለን የምታረጋግጥበት ጊዜ ቀርቧል፡፡ ጦርነቱን ሊነጋጋ ሲል እንጀምራለን፡፡" ሲል አከለለት፡፡

# ፴

ግዙፉ የመንገደኞች አውሮፕላን አዲስ አበባ ቦሌ ዓለም አቀፍ አውሮፕላን ማረፊያ ለማረፍ በማንዣበብ ላይ ነው፡፡ ኪራኮስ ቁልቁል ተመለከተ። አዲስ አበባ የተደፋ ቆሎ መስላለች፡፡ እንደለማኝ ጥሬ ዝብርቅርቅ ያለች ከተማ፡፡ከተዋቡ ፎቆችዋ ጥግ የከሰመኑና ጣራቸው ላይ ድንጋይ የፈሰሰባቸው ቤቶች፡፡ በፍሎረንስና በአዲስ አበባ መካከል ያለው ልዩነት የሰማይና የምድር ያህል ሆነበት፡፡ እስከ አሁን ያልለቀቀው ሀዘን ልቡን ባያኮማትረው ኖሮ ስለ ሁለቱ ከተሞች ልዩነት ብዙ ያስብ ነበር፡፡

ሆኖም የሊሊያ ሞት አእምሮውን እንደደረቀ ቅጠል ከሽሽ አድርጐታል፡፡ አልሞ ተኳሹ ለእርሱ የደገሳትን ድግስ ተቋድሳ ሞቱን የሞተችለት ሊሊያን ሊረሳት አልቻለም፡፡ ከመስኮቱ ቆሞ ሲያያት መስኮቷን ከፍታ ስትመለከተው በዓይነ ህሊናው እየተሳለች አስቸገረችው፡፡ አልሞ ተኳሹ በመስኮቱ ብቅ ያለው ኪራኮስ መስሎት ሳያወላውል እንደተኮሰ ጠርጥሯል፡፡ በመስኮቱ አቅጣጫ ወደ እርሱ እንደዞረች ነበር የመታት፡፡ በመጨረሻ በጣር የተናገረችው አንድ ቃል ብቻ ነበር፡፡ "እምልጥ..." የሚል ቃል ብቻ፡፡

ኪራኮስ ከዛ በኋላ በመስኮቱ ብቅ አላለም፡፡ አልሞ ተኳሽ ከማዶ እንዳለ ለመገመት ጊዜ አልፈጀበትም፡፡ አልሞ ተኳሹ ኪራኮስን እንደገደለ በማመን ስናይፐሩን ፈታቶ በሻንጣው በማስገባት ከአካባቢው ወዲያው እንደሚሰወር በማመን ነበር ኪራኮስ በፍጥነት ቤቱን ለቆ የወጣው፡፡ ሊሊያን ግንባሯን ስሞ ከመሰናበት በቀር ሊያደርግ የቻለው ነገር አልነበረም፡፡ ከዚያ በላይ የሚያደርግበት ጊዜ እንደሌለውም ያውቀዋል፡፡ ለፖሊስ ደውሎ ቢያሳውቅ ጉዳይ እስኪጣራ በቁጥጥር ሥር ላለመቆየቱ እርግጠኛ አልነበረም፡፡ ከዚህ አልፎም ጉዳይዋ እንደሆነ ተጠርጥሮ ወህኒ ቤት ሲማቅቅ ሊኖር እንደሚችልም ገምቷል፡፡

ከዚህ ሁሉ ጣጣ ውስጥ ከመግባቱ በፊትና ነገሮችም እየተወሳሰቡ ከመምጣታቸው አስቀድሞ ፍሎረንስንና ቤቱን ተሰናብቶ መውጣት ጊዜ የሚሰጠው ጉዳይ ሆኖ አላገኘውም፡፡ ተራራውን የማዳን ቁልፍ በእጁ ከመሆኑም በላይ ድርጅቱ ውስጥ በረቂቅ መንገድ ሰርገው ከውስጥም ከውጭም የሚያስጨፈጭፋትን የሚያጋልጠው ሰነድም በእጁ ይገኛል፡፡ በጋሙሶች አንገት የሚያጠልቀው ገመድም በእርሱ እጅ ብቻ እንደሚገኝ ያውቀዋል፡፡ ገመዱም ያባቱ ማስታወሻ ነው፡፡ ቁልፉም ተራራውን ማዳኛ ብቻም ሳይሆን ወደ ጋሙሶች፣ የማያስገባውን በር መክፈቻም እንደሆነ ተገንዝቧል፡፡ ጦርነቱን ከመጀመራቸው በፊት ይህን ቁልፍ ይዞ ወደ ተራራው ለመግባት ከመቸኮሉ የተነሳ የሚቀጥለውን አውሮፕላን ተሳፍሮ ወደ ባህር ዳር የመሄድ ሀሳብ ነበረው፡፡ ነገር ግን፣ በዚህ ቀን የበረራ ፕሮግራም እንደሌለ የተገለፀለት የመጣበት አውሮፕላን አርፎ ወዲያው ወደ ቢሮ ገብቶ ከጠየቀ በኋላ ነበር፡፡ አነስተኛ ቦርሳውን በትከሻው እንዳንጠለጠለ ከቦሌ አውሮፕላን ማረፊያ በጥድፊያ ወጥቶ ባለ ቢጫ ቀለም ታክሲ ተኮናተረና ወደ ለገሀር አቀና፡፡ በአነስተኛዋ ቦርሳ ውስጥ ከአባቱ ማስታወሻና ቁልፍ በቀር ሌላ ነገር አልያዘም ማለት ይቻላል፡፡ በዚች ቦርሳ ውስጥ ሊያዳብል የቻለው ልብስ እንኳን አልነበረም፡፡ ያጠራቀማትን ጥቂት ገንዘብና አንዳንድ የግል ሰነዶቹን ብቻ አክሎባታል፡፡

ለገሀር እንደደረሰ ሒሳቡን ከፍሎ ቢጫውን ታክሲ ካሰናበተ በኋላ፣ ከአንዲት አነስተኛ ሱፐር ማርኬት እሽግ ለስላሳ መጠጥና ለስለስ ያለ ዳቦ ገዝቶ እየተጓዘና እየበላ ቴሌ ባር ደረሰ፡፡ ከቴሌ ባር ፊት ለፊት ከሚቆሙት መኪናዎች አንድ ላንድክሩዘር ከተከራየ በኋላ ወዲያውኑ ሹፌሩን ወደ ባህር ዳር እንዲያከንፈው አዘዘው፡፡ የሚመቸው ከሆነ በዚሁ መኪና አዲስ ዘመን ድረስ ለመዝለቅ አስቧል፡፡ ለደህንነቱ አስጊ መስሎ ከተሰማውም፣ ባህር ዳር ወይም ሌላ ከተማ ላይ ይህን መኪና አሰናብቶ ሌላ ለመኮናተር አበክሮ አቅዷል፡፡

# ፴፭

ሚራዥ ጣቅርን ከተራራው ጫፍ ላይ በደረቱ ለጥ ብሎ በወታደራዊ መነጽር ቁልቁል ተመለከተ፤ ገና ጎህ አልቀደደም ነበር። ሰዓቱን አዩ፤ ገና መንፈቀ ሌሊት ነው። ከቧን ጨረቃ ቀና ብሎ ተመለከታት። ጥቁሩ የደመና ባዘቶ ሊውጣት ስንዝር ያህል አልቀረውም። ከባድ ዝናብ እየመጣ እንደሆነ ያስታውቃል። ከጥቁሩ ደመና ውስጥ ምልቅጥ ምልቅጥ የሚለው ሰማይ የባሪያ ድድ ይመስላል። ሰማዩን ለምን እንደሚመለከት አልገባውም። ዶፍ ዝናብ ለማን እንደሚጠቅም አልተገለፀለትም። ምልቅጥ ምልቅጥ ሲል ፍሙን የሚጥል የጋመ ግንዲላ ይመስላል። ሚራዥ ፍሙ ማን ላይ ሊወድቅ እንደተዘጋጀ አልገባውም። ጉርምርምታውና ነጎድጓዱ ሆድ ያሸብራል።

ጨረቃዋን ገና ጥቁሩ ደመና አልሰለቀጣትም። ወደ ምስራቅ በኩል የተራራው ጥላ በመውደቁ በዚያ አቅጣጫ ያለው እንቅስቃሴ አይታየውም። የሰማዩ አገጭ የተመረኮዛቸው የሚመስሉት የሊቦ ገመገሞች ሸለቆው አጥቁረውታል። ከፊት ለፊቱ ስድስት ኪሎ ሜትር ያህል ርቃ የምትገኘው የአዲስ ዘመን ከተማ ትጨላሞሳለች።

የመጀመሪያውን ምላጭ የሚስበው አልታወቀም እንጂ፤ መሳሪያው ከወዲያም ከወዲህም እሣት ለመትፋት አቆብቁቧል።

በተራራው ወገብ ላይ እንደ ዝናር የዞሩት ምሽጎች ወይ የድል ችቦ ሊበራባቸው አሊያም ወደ መቃብርነት ተለውጠው አስከሬን ሊከማችባቸው አፋቸውን ከፍተዋል። ውስጣቸው በሹክሹክታና በኖረ ጥይት ሽታ ታውዷል። በየአምስት ሜትሩ ርቀት መሳሪያውን ወድሮ ትእዛዝ የሚጠባበቅ ተኳሽ ዓይኑን ጉልጉሎ ከንዱን ወጥሮ አድፍጧል።

ጋር በጠንካራ መትረየስ ተኳሽ ሚራዥ የተራራውን ጥግና ጥግ በጠንካራ መትረየስ ተኳሽ መሣሪያ አሳጥሯል፡፡ አስጠብቆ መሀሉን በባለ ነፍስ ወከፍ መሣሪያ አሳጥሯል፡፡ ከብ ተሠርቶ እንጨት የመትረየሶች ምሽግ በግማሽ ጨረቃ ከብ ተሠርቶ እንጨት ተረብርቦበታል፡፡ የውጤት ርቀታቸው እስከ መቶ ሜትር ከሆኑት መትረየሶች ውስጥ በስተምዕራብ በኩል ያለውን ምላጭ የጨበጠችው ሲጻራ ናት፡፡ ሳዶፍና አንጎታ የውጤት ርቀታቸው እስከ ስምንት መቶ ሜትር የሆኑ ስናይፐሮችን አቀባብለው ይዘዋል፡፡ ለስብስብ ኢላማ፣ ለታንክና ለምሽግ ማውደሚያ የሚያገለግለውንና ላውንቸር የተባለውን መሣሪያ መተኮስ የሚችል ሰው ማርዬ ዋቆ ማርዬ ብቻ በመሆኑ ሁለት ቁምቡላዎች በከረጢት አንግቶ ከኋላ ተሰልፏል፡፡

ቁምቡላዎች (የላውንቸር በቆሎ እሸት የሚመስሉትን ሌላ ሶሶት ቁምቡላዎች (የላውንቸር እርሳሶች) ጨቅላ ይመስል በአንቀልባ አዝሎ አድያም እስኪለው ይጠባበቃል፡፡ የማርዬ ረዳት በመሆኑ አጉርስ እስኪለው በመጠባበቅ ላይ ነው፡፡ ላውንቸር፣ በትከሻ ላይ የሚሸከሙት ነፍጥ ሆኖ ሲተኮስ ተቀምጦ እግርን በማቆላለፍ፣ በቁም ከሆነም ግራ እግርን በማስቀደም ነው፡፡ አረሩ ከፍተኛ በመሆኑ ወደኋላ ወላፈኑ እስከ 25 ሜትር ስለሚጋረፍ ፊት ያበላሻል፡፡ ሲተኮስ አድያም እንዴት መሆን እንዳለበት ማርዬ ደጋግሞ ሲያስጠናው ቆይቷል፡፡ "ስማ እንጂ ማርዬ?"

"ወዬ?"

"ይህን አምስት ጥይት ብቻ ያለው መሣሪያ ይዘን ጥይት ሲያልቅብን ምን ሊውጠን ነው?"

"ይህም መገኘቱ ተአምር ነው፡፡ አባቶቻችን ጠንቃቆች ሆነው እነዚህን መሣሪያዎች ባያስቀምጡልን ኖሮ ይኸኔ ምን እንደምንሆን ይታይህ፡፡"

"እረ ለመሆኑ... መንግሥት የመገልበጥ ዓላማ ነበራቸው እንዴ?"

"እንደዛ እንኳ አልነበረም፡፡ ሆኖም በድርጅቱ ላይ አንድ ቀን ከውስጥም ሆነ ከውጭ አደጋ እንደሚጋረጥ ስጋት ነበራቸው፡፡"

"ለመሆኑ ይህ መሣሪያ ምን ያህል ርቀት ይወነጨፋል?"

"አምስት መቶ ሜትር ርቀት ድረስ ያለውን ስብስብ ኢላማ አመድ ያረጋል፡፡"

"ምንድነው ስብስብ ኢላማ?"

"የተሰበሰበ ኃይል ወይም ከባድ መሣሪያ ምሽግ፣ ታንክና መኪና ... ይበታትናል፡፡ የጥይቶቹ ብዛት ጥቂት መሆናቸውን አትይ፡፡ ቆጥቤ ነው የምጠቀማቸው አይዞህ፡፡ ፈሪ ነህ እንዴ?"

"እኔ ጦርነት በፊልም እንጂ በዓይኔ አይቼ አላውቅም፡፡ የካዛንቺዝ ልጅ መሆኔን ረሳኸው እንዴ? እዛ ብርጭቆና ጠርሙስ ሲሰበር ከመደንገጤ በቀር በጥይት ደንግጬ አላውቅም፡፡"

"አይዞህ... ወንድ ልጅ ሁሉን ነገር ማየት አለበት፡፡ ሕይወት ሁሉን ነገር የምንቀምስባት ጭልፋ ናት፡፡"

ከዚህ ሌላ እንደ ላውንቸሩ ሁሉ አንድ ተኳሽ ብቻ ይኑረው እንጂ፣ ዲሽቃ የሚባለው መሣሪያ ከድርጅቱ መጋዘን ተገኝቷል፡፡ ጥይቱ ከመትረየስ ከፍ ከአየር መቃወሚያ አነስ ብሎ ረዘም ያለው ይኸው ዲሽቃ የሚባል መሣሪያ ካዝናው ስልሣ ጥይቶቹን ጐርሶ የሚረግጠውን በመጠባበቅ ላይ ነው፡፡ እንደ አንዳንድ ሰው ካልኮረኮሩት የማይስቀው ይህ ዲሽቃ የተባለ ነፍጥ በወሳ እግሩ እንፈራጦ ቁሞ በመናጥ ላይ ነው፡፡ እስከ አንድ ሺህ ሜትር ያለውን ቦታ በመሣሪያው መነጽር የሚያማትረው ተኳሽም ሊያስቀው ተዘጋጅቷል፡፡ብዙ ሰው በአንድ ትንፋሽ የሚያስቀረውን ይህን መሣሪያ የኢትዮጵያ ወታደሮች በትከሻ የሶማሊያ ወታደሮች በመኪና ጭነው ሲሸከሙት የሚታወቅ ነው፡፡ የልብ አድርስ ይሁን እንጂ ሸክሙ አይጣል በመሆኑ ይዞ ለመፈርጠጥ አዳጋች ነው፡፡

ሚራዥ በሩቅ አቅራቢ መነጽሩ ቁልቁል ረባዳማውን ቦታ በሚያስስበት ወቅት፣ ዣንጊዳ እየተጣደፈ መጥቶ ከባድ መርዶ አረዳው፡፡

"ጉድ አረጉን ሚራዥ! ጉድ አረጉን!" የዣንጊዳ ፊት እንደ ሐምሌ ጨላልሟል፡፡

"እነማን ናቸው ጉድ ያረጉን?!"

"አንተማ ቀድመህ ጠርጥረህ ነበር፡፡"

ሚራዥ ስማቸውን መጠየቅ አላሻውም፡፡

"ጠፉ ነው የምትለኝ?!"

"አይደለም.....አይደለም!"

"ታዲያ ..."

"ወፎቹ እንዲለቀቁ ለማዘዝ ወደ ቴክኒክ ክፍሉ ስገባ የቴክኒክ ክፍሉ ተገድሎ አገኘሁ፡፡ ዘቦቹም ተገድለዋል፡፡ ዴር33ን ሊያበር የተዘጋጀው ሲራጅ አህመድ ሲራጅም ተገድሏል፡፡ በፍጥነት ወደ ሻጊዝ ቢሮ ስበር ገባሁ፡፡ ቢሮው ክፍት ነበር፡፡ ተተረማምሷል፡፡ ተመሰቃቅሏል፡፡ የጥቂሩ ሳጥን በርሳም መሬት ላይ ተዘርግፏል፡፡ ከሻጊዝ ቢሮ ወጥቼ ቆስሎ ወደሚያጣጥረው ዘብ ሄጄ ስጠይቀው አክሎግና አያና ሻጊዝን አግተው ጥቂሩን ሳጥን ይዘው እንዳመለጡ ነገረኝ፡፡ ታዴዎስ ኢያሱንም ፈትተው ይዘውት ሄደዋል፡፡"ዣንጊዳ ወላፈን የወበቀው ትንፋሹን ለቀቀ፡፡ ሚራዥ በእጅጉ ደነዘዘ፡፡

# ሸ፲፪

## አዲስ ዘመን

ትንሿን ከተማ ታላቅ ወሬ ሰሞኑን ሲንጣት ሰንብቷል፡፡ ብዙ ወዘልውጥ ሰዎች በከተማዋ መታየት ጀምረዋል፡፡ መጠጥ ቤቶች ሥራ በሽ መሆኑን ሲያወሩ ሰንብተዋል፡፡ ከዚህም ሌላ የሚናፈስ አሉቧልታም ከተማዋን በመናጥ ላይ ነው፡፡

"ለምንድን ነው ልጄ ?"

"እኔ ምን አውቃለሁ አየዋ! እንግዲህ እሱ ያመጣውን እሱ እስኪመልሰው ከመጠበቅ በቀር ምኑን አውቀን?!"

"እንደወሬውማ አርበኞች ግንባር የሚባል ሽምቅ ተዋጊ ጣቅርን ላይ መሽጓል ነው የሚባለው!... አርበኞች ከዚህ በኋላ እስከ አራት ኪሎ የሚያቆመኝ ኃይል አይኖርም ብሏል አሉ፡፡"

"ኧረ ተው? በምን አቀመቱ አየዋ?!"

"እኔ ምን አውቃለሁ ... ብቻ ግን እንደዛ ብሏል አሉ፡፡"

"ጉራ ብቻ እንዳይሆን እንጂ ... እስቲ ሙዚቃውን ጨመር አርጊው እቴዋ?"

"አየዋ እንጂ....."

"ወዬ....."

"ጣቅርንን የከበበው ያካባቢ ሚሊሻ ነው ወይስ ጦሩ ነው?!"

"ጦሩ ነው የሚባል እሱስ!.... ያካባቢ ሚሊሻውንማ ያቺን ሽመሌን ቢመልሱልኝ እኔ እበቃው አልነበር!... ታዲያ ምን ያረጋል... ጠብመንጃችንን ወሰዱ... ዱላችንንም ቀሙን!... እንደሴት ባዶ እጃችንን እንድንሆን ፈረዱብን..."

"ጌታው ወጥ ረገጡ!" አለ ከጥግ ለብቻው የተቀመጠ ሌላ ከተሜ ሰው፡፡ "እንደ ሴት ሲሉ ምን ማለትዎ ነው? የእነርሱ ጊዜ መሆኑን ዘነጉት እንዴ? እቴዋ እንኳዋ ጠላ ቤት የከፈቱት ከማይክሮ ወስደው አይደል!? ከ1997 ዓመተ ምህረት ወዲህ ኢህአዴግ፡ደርግ ያልተጠቀመበትን የብሔር ብሔረሰብ ጥያቄ ይዞ መንገታገቱ አላዋጣው ሲልና እንደፈንጂ ሊፈነዳ ሰዓት

ሲቆጥር፣ እሱን አንሸራቶ ሌላ የመደብ ትግሎችን ጀምሯል፡፡ የሴቶች ጉዳይ፣ የህጻናት ጉዳይ፣ የወጣቶች ጉዳይ የሚሉ ጉዳዮችን አንስቶ ሀገሩን ሁሉ ጉዳይ በጉዳይ አድርጎታል፡፡ በ1997 ወጣቶችን ድንጋይ ወረወራችሁብኝ ብሎ እያፈሰ በረሀ እንዳልወረወራቸው፣ አሁን ነገሩ ሲገባው በሊግ እያደራጀ 'ጥቃቅን እና አነስተኛ' የሚል የሥራ ስሜትን የሚገድልና ለጆሮ የሚቀፍ ስም በመስጠት አበድሯቸዋል፡፡ ሴቶችንም ከማይክሮ አበድሯል፡፡ ብድር ስላለባቸው ሌላ ፓርቲ መደገፍ አይችሉም፡፡ ከደገፉም 'እያንዳንድሽ የምትደግፊው ፓርቲ ሲያበድርሽ እናያለን' ተብለው ለማምገማ ይቀርባሉ፡፡ በ2002 ምርጫ ሴቶች ያለማንም ተቀናቃኝ ብቻውን ይወዳደር የነበረውን ገዢ ፓርቲ ለመደገፍ በነቂስ ሰልፍ ወጥተው መንገዱን ሁሉ በመዝጋት አላሳልፍ ብለው ነበር፡፡ የእኔም እናት ያለ የሌለ ክት ቀሚሷንና ኩታዋን ለብሳ እኔን እየጎተተች ወደ ሰልፉ ወጥታለች፡፡ እርሷ ከማይክሮ ስለተበደረች ነው፡፡ እኔ ግን አሻፈረኝ ብልም ልትለቀኝ አልቻለችም፡፡ ለምን ስላት ሥራ ይሰጡሀል ስትል ነበር የመለሰችልኝ፡፡ በህፃናት ፓርላማዎች ልጆች እንደጠቅላይ ሚኒስትሩ ለማውራት እንጭጭ ጉሮሮአቸውን ሲፍቁ ይውላሉ… በመደብ ማደራጀቱ ቀጥሏል፡፡"

"ሰውየ! መደብ መደብ ትላለህሳ? ከተናገርከው ሁሉ የገቡኝ ጥቂት ነገሮች ናቸው፡፡ ጉልት ማለትህ ነው ወይስ የጭቃ መደብ ማለትህ ነው? ዝም ስንልህ ብዙ አወራህ፡፡ እኛስ ብንሆን ለሽመላችን መገፊፍ ብቆረቆር ወንጀል ነው?"

"ማለቴ እንደሴት ባዶ እጃችንን ማለትዎ ተገቢ አይደለም የሴቶችን መብት መንካት ነው ማለቴ ነው!"

"አይ መበጥበጥ! እንግዲህ እኛ እንደናንተ አልተማርን! መንግሥቱ ኃ/ማርያም በየዛፉ ስር ካስቆጠረን ፊደል በቀር ምን እናውቃለን! እናንተ ከማስተማር ይልቅ ንቀታችሁ ይቀድማል፡፡ የማይገባንን የፈረንጅ ቃል እያንበለበላችሁ ሰብስባችሁን ትውላላችሁ፡፡ የምትማሩት ስብሰባ ነው፡፡ በዛ ላይ ንቀታችሁ አይጣል! አሁን እኔ እንደሴት ባዶጃችንን ስል ሴቶችን ለመናቅ ነው? አይደለም! ይህንን ሴቶችን ብትጠይቅ በደንብ ይነግሩሀል፡፡ ከሽመሌ መቀማት የተነሳ የተናገርኩት እንጂ ሌላ ትርጉም የለውም፡፡……"

ወደ አዲስ ዘመን ከተማ የሚመጣ ባላገር፣ ወደ ከተማዋ ሽመል ይዞ እንዳይገባ ከተከለከለ ቆይቷል፡፡ በመሆኑም በከተማዋ መግቢያዎች የዱላ ማስቀመጫ ቤቶች ተበጅተዋል፡፡ በታች የፎገራ፣ በላይ የሊቦ፣ የእብናት፣ የደረጣ፣ የማንቶገራ.... ባላገሮች ወደ ከተማዋ ሲገቡ ሽመላቸውን የሚያስቀምጡበት ወዳጅ ወይ በክፍያ እየተቀበለ ሽመል የሚሰበስብ ደምበኛ ያበጃሉ፡፡ ወደ አዲስ ዘመን ከተማ መግቢያ ላይ ያሉ ጠላ ቤቶችም ከጠላ ሽያጩ በተጨማሪ በሽመል ማስቀመጥ ገቢ ማግኘት ከጀመሩ ቆይተዋል፡፡ አዲስ ዘመን ውስጥ ዱላ በተለይም ባለ ጀንፎ ሽመል ትከሻው ላይ ጣል ያረገ ባላገር ማየት ብርቅ ነው፡፡ ከተገኘም ወዲያውኑ ሽመሉን ፖሊስ ይገፈዋል፡፡

ዱላ ለምን ተከለከለ ለሚለው ባለላገሮቹ የተለያዩ ምክንያቶችን ያቀርባሉ፡፡ ከፊሉ 'ቅዳሜ ቅዳሜ አዲስ ዘመን ከተማ በሽመለኞች ደም በደም ስለምትሆን ነው' ሲል፣ ከፊሉ ደግሞ 'መንግሥት ሽመል ይዘንም ስለፈራን ነው፤ የደረጣን፣ የማንቶገራን፣ የሊቦንና የከምከምን ሽመለኞች ጠብመንጃ የያዘ ፖሊስ እንኳን ስለማይችላቸው ነው' ይላል፡፡

ኪራኮስ ከጥግ ተቀምጦ የሁለቱን ባላገሮች ወግ ጥረቃ ያዳምጣል፡፡ ለይስሙላ የሚጎነጨው ቀዝቃዛ ቢራ በጉሮሮው ሲያልፍ እየፈላ የሚወርድ መሠለው፡፡

ከደቂቃዎች በኋላ ሌላ ሁለት ባላገሮች ገብተው ከእርሱ ጥግ ተቀመጡ፡፡ የለበሱት ጉጃም አዘነ አዲስ ከመሆኑም በተጨማሪ በተጫሙት በረባሶ ዘልቀው የሚታዩት እግሮቻቸው እንሶስላ ይመስላሉ፡፡

"እንዲህ ያለ ባላገርም አለ?" ኪራኮስ የባላገሮቹን ሁኔታ አይቶ ተገረመ፡፡ አንደኛው ባላገር ሠረቅ እያደረገ ያየዋል-ኪራኮስን፡፡

ከትንሽዋ መሸታ ቤት ፊት ለፊት በከተማዋ ውስጥ አለ የሚባለው የምሽት ክበብ ይገኛል- ማኪሻ ባር፡፡ ከማኪሻ ባር ፊት ለፊት ሶስት መኪናዎች ቆመዋል፡፡

ገብተው ከኪራኮስ ጐን የተቀመጡት ሁለት ባላገሮች መኪኖቹ እንዲታዩአቸው ሆነው ነው የተቀመጡት፡፡ ከማኪቫ ባር የሚንበቀበቀው ዘመናዊ ሙዚቃ እስከዚችኛዋ መሸታ ቤት ድረስ ዘልቆ ይሰማል፡፡ እዚህችኛዋ መሸታ ቤት የተከፈተው ሀገርኛ ዘፈን በዘመናዊው ላለመዋጥ ይታገላል፡፡

"....ሰው በላ

ሰው በላ

ጐራዴው ሰው በላ!..." የሚለው ሙዚቃ ተለቋል፡፡

"እስኪ ሙዚቃውን ጨመር አርጊው እቴዋ?!" አለ ሲጠጡ ከቆዩት ባላገሮች አንዱ እየነሸጠው፡፡ የሙዚቃው ድምፅ ተጨመረ፡፡

"... ሰው በላ

ሰው በላ

ጐራዴው ሰው በላ....."

⁂ ⁂ ⁂

በማኪቫ ባር ምሽቱ ከምንግዜውም በላቀ ሁኔታ ደመቅ ብሏል፡፡ ለአዲስ ዘመን ከተማ ወዘልውጥ የሆኑ ሶስት ግለሰቦች ውስኪያቸውን ሲኮመኩሙ ካመሹ በኋላ ሞቅ ሞቅ በማለታቸው ዳንኪራ ጀምረዋል፡፡ በባሩ ውስጥ የሚገኙትን ቆንጆ ቆንጆ ኮረዶች ጉያቸው ውስጥ ወሽቀዋል፡፡

እንደ ዘንዶ እየተጥመለመሉ ሲደንሱ፤ ከጉያቸው የወሸቁት ሽጉጥ ሳይቀር ሊደበቅ አልቻለም፡፡

⁂ ⁂ ⁂

ከማኪቫ ባር ፊት ለፊት ያለችው መሸታ ቤትም ያቅሟን በመጋል ላይ ናት፡፡
ሙዚቃው ተቀይሯል፡፡

"... የሸምብራው ጥርጥር የዛፎቹ ፍሬ

የትም የትም ዞሬ ትዝ አለኝ አገሬ…"

"እቴዋ ድምፁን ጨምሪው እንጂ… ያዝ እንግዲህ……"

ሁለቱ አዳዲስ ጉጃምአዘነ ለባሾች ወሬያቸው በሹክሹክታ በመሆኑ ለኪራኮስ ሊሰማው አልቻለም፡፡ ብዙ አይነጋገሩም፡፡ ከተነጋገሩም በለሆሳስ ነው፡፡

"ጌታው እንተዋወቃለን ልበል?" ሲል እንደኛው ከጥጉ ያለው ባላገር ኪራኮስን ጠየቀው፡፡ ኪራኮስ የባላገሩን ፊት ለማጤን ሞከረ፡፡ ከዚህ በፊት አይቶት የሚያውቅ መሰለው፡፡

"ምናልባት ተመሳስዬብዎ እንዳይሆን…" ኪራኮስ ራሱን በአሉታ ነቅንቆ መለሰለት፡፡ እንደገና ዝምታ ሆነ፡፡

"….የሽምብራው ጥርጥር የዛፎቹ ፍሬ
የትም የትም ዞሬ ትዝ አለኝ አገሬ….."

"ትዝ አለኝ" የሚለውን አዝማች እየተቀበሉ ሙዚቃውን አስደገሙት፡፡

"…ዳገት ቁልቁለቱን፣ ስንወጣ ስንወርድ
ኮለል ካለው ሜዳ፣ ከብቶች ስናግድ
ያ ሁሉ ቀረና፣ ቁም ነገር መጣና
ትምህርት ቤት ገባን፣ ፊደል ልናጠና
ከሁሉም ከሁሉም የሚለኝ ደስ ደስ
ክረምት ዝናብ ሲሆን ገሳ ስንለብስ…"

"ኪራኮስ" አለው ከጥጉ ያለው ባላገር ከአያሌ የዝምታ ደቂቃዎች በኋላ፡፡ "ራስህን ለአደጋ አጋልጠሀል፡፡"

ኪራኮስ ከው ብሎ ባላገሩን ተመለከተው፡፡ ምስሉ መጣለት፡፡ ድምፁንም ከዚህ በፊት ሰምቶታል፡፡

"ተከተለን፣ መውጣታችን ነው፡፡ አደጋ ላይ ነህ፡፡" ሁለቱ ባላገሮች አንድ ላይ ተነሱ፡፡

ማኪሻ ባር ውስጥ ሳቅ በርክቷል፡፡ ከሶስቱ ወዘልውጦች አንደኛው በእንግሊዝኛ ስልክ እያናገረ፣ ፈጠን ብሎ ወጥቶ ከጥቂት ደቂቃዎች በኋላ ተመለሰ፡፡

"ሮበርት ጋሎ ነው፡፡" አላቸው ለሁለቱ ጓደኞቹ ተንቀሳቃሽ ስልኩን ወደ ኪሱ እየከተተ፡፡ "ፈንጥዟል፡፡"

"አክሎግ!...አያና!.... ጠጡ! ለፈፀማችሁት ጀብዱ መጠጣት ያንሳችኋል፡፡" አለ ብርጭቆውን ከፍ አድርጎ፡፡

"ሜሮዳን ግን እንዴት ልትይዛት ቻልክ?... እውነትም ቀንጠፋ" አለው አክሎግ ብርጭቆውን ከብርጭቆው እያጋጨ፡፡

"ቀን ጥሏት ነው፤ ቀን የጣለው ምን ጉልበት አለው?..."

"ለምን እዚህ ድረስ ይዘሀት መጣህ?"

"ገና በየሄድኩበት ይገፐት እዞራለሁ፡፡ ለጉራም ለዝናም የምትሆን ምርኮኛ እኮ ናት! በዛ ላይ አንዳንድ ምስጢሮችን ታሾልክልኛለች የሚል ተስፋ ስለነበረኝ ነው፡፡ ሆኖም ገልብጬ ብገርፋትም ትንፍሽ ልትልልኝ አልቻለችም፡፡ ግን አንድ ነገር ገርሞኛል!"

"ምን?!..."አለ አያና ዝም ብሎ ሲያዳምጥ ቆይቶ፡፡

"ቆንጆ ሴት የማሰቃየትን ያህል ደስታ የሚሰጥ ነገር የለም፡፡...ሃሃሃ..."

"ሃሃሃ..." ሶስቱም ቀንጠፋውን ተከትለው ሳቃቸውን ለቀቁት፡፡

"አቤት! አቤት!... ቁንጅናዋ ቁንጅና መሰላችሁ እንዴ?......ታስጎመጀለች!..."

"ታዲያ እዚህ ከተማ ውስጥ የት አሰርካት?" አክሎግ ጠየቀው፡፡

"ፖሊስ ጣቢያ የምከታት ይመስልሃል? ያችን የመሰለች ቆንጆ ከኔ በቀር ሌላ ሰው እንዲመረምራት የምፈቅድ ይመስልሃል? ይልቁንስ ቶሎ ቶሎ ጠጡ መሄዴ ነው፡፡ ወዴት ነው የምትሄደው?....."

"ወደ እርሷ ነዋ! .... ጦርነቱ ከመጀመሩ በፊት የማናግራት ጉዳይ አለ..."

"..... ይህቺ ነገር ... " አለ አክሎግ፡፡ "ሌላ ነገር መመርመር ጀመርክ እንዴ?"

"ማለት .... "

"ገብቶሃል .... "

"ሃሃሃ... ደርጎች የጋለ ብረት ይከቱበት የነበረውን ነገር ማለትህ ነው? ...ሃሃሃ.... ስማ'ንጂ .... ስንት የጋለ ነገር እያለን ....ሃሃሃ..... " ቀንጠፋው ደረቅ ሳቁን ሲለቀው ሁለቱም ተከትለውት ተንፈቀፈቁ፡፡ "ከፎርሙላ በቀር ምንም የማያውቅ ኢንጂነር ይዛችሁ... ከያዙ አይቀር እንደ ሚሮዳ ያለ ቆንጆ መያዝ ነበር እንጂ!... ለማንኛውም ጦርነቱ ከመጀመሩ በፊት ወደ እርሷ መሄዴ ነው፤ ከእርሷ ጋር ሌላ ጦርነት አለብኝ፡፡ የኢንጂነሩ ጠባቂዎች ግን ይጨመሩ፡፡ ሮበርት ጋሎ ከአዲስ አበባ ተነስቷል፡፡ ሊነጋጋ ሲል መድረሱ አይቀርም፡፡"

"ባዶ እጁን እንዳይመጣ ንገረው፡፡ ሲ.አይ.ኤዎችን ማመን አይገባም፡፡ ክፍያውን ሳይፈፅም ኢንጂነሩንም ሳጥኑንም ባይኑ ማዬት አይችልም፡፡ ....ንገረው፡፡"

"ችግር አይግባችሁ፡፡ በገንዘብ የተጎጠረውን ሳምሶናይት ሳይዝ ከአዲስ አበባ አይነሳም፡፡" አለ ቀንጠፋው ወደ ሁለቱም አጎንብሶ ፈገግ እያለ፡፡ "የጋለ ብረት ይዞ ከቆመ ሰው ጋር ረጅም ወሬ ማውራት ኃጢአት ነው፡፡ እኩለ ሌሊት እየሆነ እኮ ነው፡፡ በሉ በጊዜ ግቡ.... ሃሃሃ.... " ቀንጠፋው ሂሳብ ከፍሎ ሊወጣ ሲል ዶፍ ዝናብ ይወርድ ጀመር፡፡ ወዲያው አንዲት ወታደሮችን የጫነች ጂፕ መኪና እየከነፈች መጥታ ከማኪቫ ባር ደጅ ላይ ከመቆሟ ጋቢና የተቀመጠው ሻለቃ በፍጥነት ወርዶ ወደ ውስጥ ገባ፡፡

ሻለቃው ወደ ሶስቱም ጆሮ ተጠግቶ "ጦርነቱን ባልጠበቅነው ሰዓት ጀምረውታል፡፡" ሲል አንሾካሾከ፡፡

"ያን ሚራዥ የተባለ ሰይጣን ወደ ገሀነም እልከዋለሁ!" አክሎግ ጠረጴዛውን ደበደበ፡፡

"ማነው ሚራዥ ?" አለ ሻለቃው ግራ እየተጋባ፡፡ ሰምቶት የማያውቀው ስም ነበር፡፡

"የአርበኞች ግንባር የአንድ ሬጅመንት መሪ ነው፡፡" አለው ቀንጠፋው ቀልጠፍ ብሎ፡፡

"እሱ ነው! እሱ ነው! ጉሮሮውን እቆርጠዋለሁ!" ሶስቱም ሻለቃውን ተከታትለው ወጡ፡፡

ꕤ ꕤ ꕤ

ኪራኮስ ሁለቱን ባለገሮች ሲከተል ከቆየ በኋላ ፍጥነታቸውን ጨምረው ተሰወሩበት፡፡ በሸኒ ወንዝ ላይ የሚያሻግረውን ጥንታዊ ድልድይ ሲያቋርጥ ዶፍ ዝናብ ይወርድበት ጀመር፡፡ ሆኖም ዳገቱን በሩጫ ተያያዘው፡፡ የዝናቡ ነጠብጣቦች ምንም ነገር ሊያሳዩት አልቻሉም፡፡ ወደ ሰሜን ምሥራቅ አካባቢ የሚንጣጣ የመሳሪያ ድምጽ የሰማ መሰለው፡፡

ቆሞ ወደዛው ተመለከተ፡፡ እንደ መብረቅ ብልጭ ድርግም የሚል ብርሃን አየ፡፡ ጦርነቱ እንደተጀመረ አረጋገጠ፡፡ በዚህ ድቅድቅ ጨለማ ወደ ጣቅርን ድረስ እንዴት መጓዝ እንደሚችል እየሮጠ ለማሰብ ሞከረ፡፡ በዚሁ ቅጽበት ከኋላው የሚራመድ ኮቴ ተሰማው፡፡ ወደ ኋላው እየሮጠ ለመዞር ሲሞክር አንዠላልጦት ሊወድቅ ሲል ለጥቂት ተንገዳግዶ ቆመ፡፡

ሁለቱ ባላገሮች ነበሩ ከኋላው የደረሱበት፡፡

"ኪራኮስ... ዘግይተሃል!"

"እነማን ናችሁ?!...." ኪራኮስ ሽጉጡን ላጥ አርጎ ፈንጠር ብሎ ቆመ፡፡

"ጌ... ጌራ ነኝ፡፡ አብሮኝ ያለው ደግሞ ኮ/ል አሊጋዝ ነው፡፡"

ኪራኮስ ሽጉጡን ወደ ሽንጡ ሻጠ፡፡

"እዚህ ምን ትሠራላችሁ?"

"አንተ ራስህ እዚህ ምን ትሠራለህ?"

"ሊነጋጋ ሲል ወደ ጣቅርን ለመሄድ እቅድ ነበረኝ፡፡"

"ጣቅርን መከበቡን አልሰማህም እንዴ?"

"መስማቱንማ ሰምቻለሁ፤... ጦርነቱ ከመጀመሩ በፊት ለመድረስ ተስፋ አድርጌ ነበር::"

"አብደሀል?!" አለው ጌራ ተጠግቶ:: "በየት በኩል ትገባለህ?!"

"እንደ እባብ በደረቴ እየተሳብኩ እንኳ ለመግባት አቅጄ ነበር:: ምክንያቱም በተራራው ውስጥ ያሉትን ሁሉ ማትረፍ የሚችለው ብቸኛ ቁልፍ በእጄ ነበር::"

"ምን አይነት ቁልፍ ነው?!"

"... ታሪኩ ረጅም ነው:: ይልቁንስ ወደተራራው የምንገባበት ዘዴ ካለ እሱን ብቻ ነው የምፈልገው::"

ከብዙ ውትወታ በኋላ ኪራኮስ የምስጢሩን ጫፍ አስያዛቸው- ከተራራው እስከ ዳጋ የተዘረጋውን የውስጥ ለውስጥ መንገድ ቁልፍ:: ጌራና ኮ/ል አሊጋዝ የሚሰሙትን ማመን አቃታቸው:: ኪራኮስን ከአዲስ ዘመን ከተማ ሰሜናዊ አቅጣጫ ወደሚገኝ የገጠር መንደር ወሰዱት::

በአንድ የገበሬ ቤት ውስጥ ከሃያ በላይ ሰዎች ታጥቀው ጌራንና ኮ/ል አሊጋዝን በመጠባበቅ ላይ ነበሩ::

"ከኋላ አስከፍተን ወደ ተራራው የመግባት እቅድ አለን:: የዴር33ን መሪ እስክጨብጥ ጓጉቻለሁ::" ሲል እቅዱን ነገረው ጌራ የባላገር ልብሱን አውልቆ ተራራውን ከከበበው ኃይል ጋር ተመሳሳይ የሆነውን መለዮ እየለበሰ:: ሌላ መለዮ አምጥቶ ለኪራኮስም አለበሰው::

"የት አገኛችሁት?!" ኪራኮስ የታጠቁትን ሰዎች ሁሉ ባይኑ እየቃኘ:: ጌራ ወደ ኮ/ል አሊጋዝ ፊቱን አዞረ:: ኮ/ሉ ተራ የወታደር ልብስ ለብሰው ቆመዋል:: ኪራኮስ ነገሩ ገባው:: ከሆነ የመሳሪያ ግምጃ ቤት፣ ያስወጡት መሳሪያ እንደሆነ ተረዳ::

ኪራኮስ ወደ ጌራ ተጠግቶ አንድ ጥያቄ ጠየቀው:: "የታጠቅነው ተራ የነፍስ ወከፍ መሳሪያዎችንና ጥቂት የእጅ ቦንቦችን ነው:: በዚህ ትጥቅ ወደ ተራራው የምንገባ ይመስልሃል?"

"የታላቁ ገጣሚ ስንኝ ብቻ ነው መልሴ ሊሆን የሚችለው፡፡ 'ከሞከርነው ነገር ይልቅ ያልሞከርነው ነው የሚቆጨኝ'...."

"ፀጋዬ ገብረ መድህን...."

"እንቀሳቀስ ጓዶች! ... ትጥቃችሁ መጥበቁን አረጋግጡ!..... ያልጠበቀ ትጥቅ ከመታጠቅ አለመታጠቅ ይሻላል፡፡" ኮ/ል አሊጋዝ የሁሉንም ትጥቅ መጥበቁን ይፈትሹ ጀመር፡፡

# ፴፫

ጣቅርን ተራራ ላይ እሳትና ዝናብ እኩል በመዝነብ ላይ ናቸው፡፡ ዶፍ ዝናብ- ዶፍ እሳት፡፡መትረዬሶች እያጓሩ፤ ክላሽንኮቮች እያሽካኩ ናቸው፡፡ ላውንቸሮች እሳት ልሰው እሳት ቀምሰው በቁምቡላቸው ፍም ጭነው ከወዲያ ወዲህ እየተራወጡ ናቸው፡፡ የጣቅርን ሌሊት በእርሳስ ብርሀን ወደ ቀንነት ተለውጧል፡፡ ዶፉ ዝናብ ከወዲያ ወዲህ የሚያፏጩትን ጥይቶች አላበረዳቸውም፡፡ ጣቅርን ሰማይዋ በመብረቅ ምድሯ በጥይት ወበቅ በመታረስ ላይ ነው፡፡

ፍልሚያው እንደተጀመረ ተራራውን ከብቦ የነበረው ኃይል ወዲያው ነበር የጦር ቅርፅ በመስራት፣ ተራራውን እንደ ጉንዳን መውረር የጀመረው፡፡ ከፊት ያለው ወታደር ዝግዛግ እየሮጠ ወደተራራው ሲወሽቅ ሌላኛውና ከኋላ ያለው የፊተኛውን ሽፋን በመስጠት ይከተላል፡፡ በዚህ ቅርፅ አጥብቦ በጥልቀት በወታደሮች መካከል ከአምስት እስከ ሰባት ሜትር ርቀት እየሰራ በማስፋት ሽቅብ ወደ ተራራው ይርመሰመስ ጀመር፡፡

ሚራዥ እንደገመተው የተራራውን ምዕራባዊ ጥግ ይዘው ነበር ማጥቃት የጀመሩት፡፡ በምዕራቡ አቅጣጫ መትረየሷን ጠምዳ አላስወጣ ያለቻቸው የሲጻራ ምሽግ የጥይት አረር ይወርድበት ጀምሯል፡፡ ላንቃቸው እስኪዘጋ የሚንተገተጉት የነፍስ ወከፍ መሳሪያዎች ሽቅብ የሚተመውን ኃይል ይለቅሙ ጀምረዋል፡፡

እንደ ቡና ቤት ሴት አስሬ ወልውሉኝ የሚለውንና ስናይፐር የሚባለውን መሳሪያ የያዘው ሳዶፍ፣ የማነጣጠሪያ መነጽሩን ደጋግሞ እየወለወለ ኢላማው ውስጥ የሚያስገባውን ይጠርዝ ገብቷል፡፡

ማርዬ ዋቆ ማርዬ ላውንቸሩን በትከሻው ተሸክሞ የበቆሎ እሸት የመሰለ ቁምቡላውን እጃቸውን ሊይዝ ወደሚጣደፈው ዘማሚት የመሰሊ መንጋ የፊት ስለትን እና የኋላ "ሆ" ቅርጽን እየጠበቀ በድምሩ "ሰ" ቅርጽን በመስራት ሰብሰብ ኢላማ እየመረጠ እሸት መላኩን ቀጥሏል፡፡ የሚፈለፍል እንጂ የማይፈለፈል እሸት፡፡ የሚበላ እንጂ የማይበላ እሸት፡፡ የሚያነድ እሸት፡፡ የሚያቃጥል እሸት፡፡

"ጥይት ቆጥቡ! ጥይት ቆጥቡ!" ሚራዥ ምሽግ ለምሽግ እንደ እባብ በደረቱ እየተሳበ ትዕዛዝ ማስተላለፉን ቀጥሎበታል፡፡ "የሚንቀሳቀስ ነገር ባያችሁ ቁጥር አትተኩሱ፡፡ አልማችሁ ተኩሱ እንጂ!......አልሞ ካለመተኮስ ጭራሹን ምላጭ አለመሳብ ይሻላል፡፡ አልሙ! ጥይት ቆጥቡ!..."

የእጅ ቦንቦች ወደ ምሽጉ ይወረወሩ ጀመር፡፡ ከታችም ከላይም ወደ ሰማይ እየቶጉ ብትንትን ብለው ወደ ምድር ሲመለሱ ዱቄት የሚሆኑ አጥንቶች፣ ቀዝቃዛውን ጎርፍ የሚቀላቀል የሚንፎለፎል ትኩስ ደም፣ የሚያጣጥር ጣረሞት የያዘው.... ተራራውን የሞት ጥላ ጎፋፈነው፡፡

ከከባድ ፍልሚያ በኋላ ከተራራው እየተርመሰመሰ ይወጣ የነበረው ኃይል፣ ቁስለኛውን እየጎተተ አስከሬኑን እየለቃቀመ ያፈገፍግ ጀመር፡፡..... የጥይቱ ኳኳታም እየቀነሰ መጣ፡፡ እንደ ቆቅ የሚያሽካኩት መትረየሶችም ትንፋሽ ወሰዱ፡፡ አልፎ አልፎ ካልሆነ በቀር ተኩሱ እየቀዘቀዘ መጣ፡፡

አካባቢውን የባሩድ ትንፋግ አፍኖታል፡፡ ምሽጉን እስከ ጭን የሚውጥ በደም የተበከለ ጎርፍ ሞልቶታል፡፡ ሚራዥ ተኩሱን ለማስቆም ከወዲያ ወዲህ ይባዝን ጀመር፡፡ ቁስለኛ አንሻዎችና አስከሬን ቀባሪዎች የምሽጉን ውስጥ ጎርፍ ያንቦጫርቁ ገቡ፡፡

ወገግ እያለ ነው፡፡ ዝናቡም ችፍ ችፍ እያለ ተንጠባጥቦ ሊቆም ተቃርቧል፡፡ ሚራዥ በሩቅ አቅርብ መነጽሩ ቁልቁል ለመመልከት ሞከረ፡፡ በስተደቡብ ምስራቅ ተራራውን አቅፎ በሚዞረው የዙንዝ ሸለቆ ውስጥ የዙንዝ ወንዝ ሞልቶ

ይጥመለመላል፡፡ ከወንዙ ወዲህ ማዶ ሸለቆው ውስጥ ለውስጥ ተራራውን ለመውረር የመጣው ኃይል ይተረማመሳል፡፡

"ምናልባት እንደገና ሊመጡ እየተዘጋጁ ይሆናል" አለ ሚራዥ መነጽሩን ለገርንጊዳ እንዲመለከት እያቀበለው፡፡

"በፍጥነት እንኳ የሚያደርጉት አይመስለኝም፡፡" ሲል መለሰለት ገርንጊዳ፡፡ "እስኪመሽ ይጠብቁ ይሆናል፡፡ ስንቃችንና ትጥቃችን እስኪያልቅ ጠብቀው እጅ እንድንሰጥ ነው የሚጠባበቁን፡፡ ስለ ስንቃችንና ትጥቃችን ከነ አክሎግ በቂ መረጃ አግኝተዋል፡፡ እነ አክሎግ ለጠርነቱ ዝግጅታችንን እስክናጠናቅቅ ጠብቀው መሄዳቸው አቅማችንን በደንብ አውቀው በየትም በኩል ማምለጥ እንደማንችል አረጋግጠው መውጣታቸውን ያረጋግጣል፡፡"

ሚራዥ በሩቅ አቅርብ መነጽሩ አካበቢውን እንደገና ያማትር ጀመር፡፡ ዝናቡ ሙሉ ለሙሉ ቆሟል፡፡ በተራሮች ራስ ላይ ግን ጉም ይንጎማለላል፡፡ ከማዶ ደረቱን ገልብጦ የቆመው የሙቃራ ተራራ የጉም ዘንዶ ወገብ ለወገቡ ይጥመለመልበታል፡፡ አቢንጋና ደብራን ይዞ እስከ ሊቦ ገመገሞች የጭጋግ ልጋግ ይኾረበረብባቸዋል፡፡ ወደ ምዕራብ ተመለከተ፡፡ የኪብራ ወንዝ ከጣቅርን ጀርባ እንደበረገገ አውሬ እየጎደረ ቁልቁል ከተወዘገዘገ በኋላ ከዙንዝ ወንዝ ጋር በመቀላቀል የሽኒ ወንዝን ይፈጥራል፡፡ ከኪብራ ባሻገር በእስጢፋኖስና በደራጣ ረባዳ ቦታዎች የተኛው ጎርፍ መስታወት መስሏል፡፡ ወደ ላይ ዜና ማርያምን ይዞ ከማንቶገራ ሸለቆ እስከ ምርጫ ደብር፣ ከአምባ ተራራ እስከ ጣራ ገዳም በጉም ተለጉሟል፡፡

ሚራዥ ራሱ የቆመበት ጣቅርን ተራራም፣ የጉም መቀነት እየዞረበት ነው፡፡ በስሱ የጉም ኩታ ውስጥ ነጭ ባንዲራ እያውለበለበ ሽቅብ ወደ ተራራው የሚወጣ ሰው ተመለከተ፡፡ አቅርቦ የሚያሳየውን መነጽር ለገርንጊዳ አቀበለው፡፡ ሚራዥና ገርንጊዳ እርስ በእርስ ተያዩ፡፡



Scanned by CamScanner

# ፴፬

## ማንቶገራ ሸለቆ

ወደ ተራራው ሳይጠጉ በመንጋቱ ማንቶገራ ሸለቆ ውስጥ መሽጎ ከመዋል በቀር አማራጭ አልነበራቸውም፡፡ ኮ/ል አሊጋዝ መንጋቱን በማየት ብቻም ሳይሆን ፍልሚያው ከወደ ተራራው ጋብ በማለቱ ነበር ትዕዛዝ ያስተላለፉት፡፡ እንደ ኮ/ል አሊጋዝ ግምት ይህ ጦርነት በሚስጢር እንዲያዝ ተራራውን የከበበው ኃይል አዛዦች ይፈልጋሉ፡፡ ትልቅ ግብግብ ገጥመው የጦርነቱ ወሬ ሀገር እንዲያዳርስ እንደማይፈልጉ ያውቃሉ፡፡ በመሆኑም ተራራው ውስጥ የመሸገው ህቡዕ ማህበረሰብ ረሀብ ሲጠናበት እጁን ይሰጣል ተብሎ በመገመቱ ከበባውን አጠናክሮ አጣጥሮ አስኪሞት መጠባበቅ አንዱ የጦርነቱ አካል ተደርጎ የተያዘ ጉዳይ እንደሆነ ገምተዋል፡፡

ጌራና ኪራኮስ ፈንጠር ብሎ ከተገጨረው ቋጥኝ ውስጥ እንደ አሽኮኮ ተወሽቀው የባኮስን ማስታወሻ በማገላበጥ ላይ ናቸው፡፡ ጌራ በማስታወሻው ተደንቆ ሊያበቃ አልቻለም፡፡ ከዓለማቀፎቹ ምስጢራዊ ማህበረሰቦች በላይ የሀገር ውስጡ ምስጢራዊ መንግስት ምስጢር ሁሉ ከማስገረም አልፎ አስደንግጦታል፡፡ የነአክሎማን ጉድ ተዘክዝኮ ሲያይ ልትገድለው ትከተለው የነበረችው ሴትም አክሎማ ከእነርሱ ጋር እንድትሠራ የመለመላት መሆንዋን አስታወሰ፡፡

ኮ/ል አሊጋዝ በሌላ ሰው ስም በወጡት አዲስ ተንቀሳቃሽ ስልክ ለረጂም ሰዓት ሲያወሩ ቆይተው ቋጥኙ ውስጥ ተወሽቀው ወደ ሚያቶክቱኩት ጌራና ኪራኮስ መጥተው ተቀላቀሉ፡፡ ሁለቱም አዲስ ነገር ለመስማት ጆሮዎቻቸውን አቆሙ፡፡

"አክሎግ ጉድ ሰርቶናል" አሉ ኮ/ሉ ሁለቱንም አፈራርቀው እየተመለከቱ፡፡ "ሻጊዝን እስከ ጥቁሩ ሳጥን ይዞት ከተራራው አምልጧል፡፡ አዲስ ዘመን ውስጥ በሚገኝ አንድ በጥብቅ የሚጠበቅ ቤት ውስጥ እያስጠበቀው መሆኑን የሚገልጽ መረጃ ደርሶኛል፡፡ በሌላ በኩል ሜሮዳም እርሱን ካገተበት በቅርብ ርቀት ላይ በሚገኝ ቤት ውስጥ ታስራ እንደምትገኝ ሰምቻለሁ፡፡ በደቂቃዎች ውስጥ እዚህ ለመድረስ የሚገሰግስ የ'ኛ ሰው የቤቶቹን አቀማመጥ የሚያሳይ ካርታ ስሎ እየመጣ ነው፡፡"

ለጥቂት ደቂቃ ፀጥታ ሰፈነ፡፡ በእልህ የታመቀ ፀጥታ፡፡ ጥርስ ያስነከሰ ዓይን ያንቦገቦገ ፀጥታ፡፡ የጌራ ትንፋሽ ወላፈን እንቁላል ይቀቅል ነበር፡፡

"ተቀደምሁ!" ኪራኮስ ጉልበቱን በማስታወሻው እየደበደበ ተነሳ፡፡

"ተቀመጥ! ተቀመጥ!" ኮ/ል አሊጋዝ ስበው አስቀመጡት፡፡

"ይህ የውሻ ልጅ አላምጠዋለሁ፡፡ አለቀውም! ... እድሜ ልኬን አሳድደዋለሁ!" ጌራ ጣቶቹን በስሜት አሾላቸው፡፡ "ምን አክሎግ ብቻ አያናስ ቢሆን!? ያ... ከሀዲ ..."

"አክሎግ እንጂ አያና እንኳ ይህን ያህል አቅም ያለው ሰው አይደለም፡፡ አያና ከአፉ በቀር ሌላ ምንም የሌለው ሰው ነው" አሉ ኮ/ል አሊጋዝ ሁለቱንም ካረጋጉ በኋላ፡፡ "ያም ሆነ ይህ አሁን በሁለት አጣብቂኝ ጉዳዮች ውስጥ ገብተናል፡፡ አንደኛው ወደ ተራራው ሄደን ሰዎቻችን መቀላቀልና ማትረፍ የሚለው ሲሆን ሁለተኛው ደግሞ ወደ አዲስ ዘመን በመግባት ኢንጂነሩንና ሜሮዳን ማትረፍ ነው፡፡"

"ማትረፍ ሲሉ..." ጌራ ወደ ኮ/ሉ አሰገገ፡፡

"ትናንት ማታ አንድ ለእኛ እንዲሰልል ከተማዋ ውስጥ ያሰማራሁት ሰው እኛ ኪራኮስን ተከታትለን ከገባንበት መሸታ ቤት ፊት ለፊት ከነበረ ባር ውስጥ ነበር ያመሸው፡፡ ማኪሻ ባር ውስጥ፡፡ ቀንጠፋው በመባል የሚታወቀው የደህንነት ቢሮው ሰው ከሁለቱ ጋር እዛው ባር ውስጥ ሲጠጡ ነበር ያመሹት፡፡ መንፈቀ ሌሊት እስኪሆን እዛው ማኪሻ ባር ውስጥ ነበሩ፡፡"

"እነማን ናቸው ሁለቱ?" ጌራ ኮ/ሉን አቋረጣቸው፡፡

"አክሎግ ጉድ ሰርቶናል" አሉ ኮ/ሉ ሁለቱንም አፈራርቀው እየተመለከቱ፡፡ "ሻጊዝን እስከ ጥቂቱ ሳጥን ይዞት ከተራራው አምልጧል፡፡ አዲስ ዘመን ውስጥ በሚገኝ አንድ በጥብቅ የሚጠበቅ ቤት ውስጥ እያስጠበቀው መሆኑን የሚገልጽ መረጃ ደርሶኛል፡፡ በሌላ በኩል ሚሮዳም እርሱን ካገተበት በቅርብ ርቀት ላይ በሚገኝ ቤት ውስጥ ታስራ እንደምትገኝ ሰምቻለሁ፡፡ በደቂቃዎች ውስጥ እዚህ ለመድረስ የሚገሰግስ የ'ኛ ሰው የቤቶቹን አቀማመጥ የሚያሳይ ካርታ ስሎ እየመጣ ነው፡፡"

ለጥቂት ደቂቃ ፀጥታ ሰፈነ፡፡ በእልህ የታመቀ ፀጥታ፡፡ ጥርስ ያስነከሰ ዓይን ያንቦገቦገ ፀጥታ፡፡ የጌራ ትንፋሽ ወላፈን እንቁላል ይቀቅል ነበር፡፡

"ተቀደምሁ!" ኪራኮስ ጉልበቱን በማስታወሻው እየደበደበ ተነሳ፡፡

"ተቀመጥ! ተቀመጥ!" ኮ/ል አሊጋዝ ስበው አስቀመጡት፡፡

"ይህ የውሻ ልጅ አላምጠዋለሁ፡፡ አለቀውም! ... እድሜ ልኬን አሳድደዋለሁ!" ጌራ ጣቶቹን በስሜት አሾላቸው፡፡ "ምን አክሎግ ብቻ አያናስ ቢሆን!? ያ... ከሀዲ ..."

"አክሎግ እንጂ አያና እንኳ ይህን ያህል አቅም ያለው ሰው አይደለም፡፡ አያና ከአፉ በቀር ሌላ ምንም የሌለው ሰው ነው" አሉ ኮ/ል አሊጋዝ ሁለቱንም ካረጋጉ በኋላ፡፡ "ያም ሆነ ይህ አሁን በሁለት አጣብቂኝ ጉዳዮች ውስጥ ገብተናል፡፡ አንደኛው ወደ ተራራው ሄደን ሰዎቻችን መቀላቀልና ማትረፍ የሚለው ሲሆን ሁለተኛው ደግሞ ወደ አዲስ ዘመን በመግባት ኢንጂነሩንና ሚሮዳን ማትረፍ ነው፡፡"

"ማትረፍ ሲሉ..." ጌራ ወደ ኮ/ሉ አሰገገ፡፡

"ትናንት ማታ አንድ ለእኛ እንዲሰልል ከተማዋ ውስጥ ያሰማራሁት ሰው እኛ ኪራኮስን ተከታትለን ከገባንበት መሸታ ቤት ፊት ለፊት ከነበረ ባር ውስጥ ነበር ያመሸው፡፡ ማኪያ ባር ውስጥ፡፡ ቀንጠፋው በመባል የሚታወቀው የደህንነት ቢሮው ሰው ከሁለቱ ጋር እዛው ባር ውስጥ ሲጠጡ ነበር ያመሹት፡፡ መንፈቀ ሌሊት እስኪሆን እዛው ማኪያ ባር ውስጥ ነበሩ፡፡"

"እነማን ናቸው ሁለቱ?" ጌራ ኮ/ሉን አቋረጣቸው፡፡

"አክሎግና አያና፡፡" ኮ/ሉ ለጥቂት ደቂቃዎች ዝም ካሉ በኋላ "ቀንጠፋው፣ አክሎግና አያና ሞቅ እያላቸው ስለመጣም ይሁን አልያ ለማንም ለምንም በዛ ቤት ውስጥ ላለ ምስጢሩ ይገበዋል ብለው ባለመገመታቸው ስለ ኢንጂነሩና ስለ ሜሮዳ ጉዳይ የለፈለፉትን ሁሉ የባላገር ልብስ የለበሰና የሰከረ መስሎ የዛለ የኛ ወኪል ሰምቷቸዋል፡፡" ስለሜሮዳ የተባለውን ጌራ እንዳይሰማ በማሰብ ስለ ሻጊዝ ያሉትን ተናገሩ፡፡

"ለሲ-አይ-ኤ. ሊሸጡት!?" ጌራና ኪራኮስ ክው አሉ፡፡

"አዎ..." አሉ ኮ/ሉ ሰዓታቸውን እየተመለከቱ፡፡ "አንድ ሮበርት ጋሎ የሚባል የሲ. አይ.ኤ ወኪል ከአዲስ አበባ ተነስቶ ኢንጂነሩንና ጥቁሩን ሳጥን ጭኖ ለመሄድ እየጋለበ ነው አሉ፡፡ ከፍተኛ ቁጥር ያለው ገንዘብም ጭኗል፡፡ የማታ ማታ አዲስ ዘመን መድረሱ አይቀርም፡፡ ስለዚህ ሽያጩ ከመከናወኑ በፊት አንድ ነገር ማድረግ አለብን ማለት ነው፡፡"

"የትኛውን እናስቀድም?" ጌራ ግራ እየተጋባ ጠየቀ፡፡ "በቀን ወደ ተራራው መጠጋት አንችልም?"

"በቀን ወደ ተራራውም ሆነ ወደ ከተማው መግባት አንችልም፡፡" ኮ/ል አሊጋዝ ሽቅብ ወደ ተራራው ተመለከቱ፡፡ በላይ የዜና ማርያም የተራራ ሰንሰለቶች ጣቅርንን ቁልቁል አቅፈውት አዩ፡፡ "በዜና ማርያም በኩል ዙረን ወደ ተራራው መግባት እንችል ይሆናል፡፡ ሆኖም ለጉዞ አመቺ ካለመሆኑም በላይ የመታየት እድላችን ቀጥታውን ከመንገዝ ጠባብ ቢሆንም፣ በባላገሮች እይታ ውስጥ መግባታችን ግን አይቀርም፡፡ ጥቆማ ከደረሰው ተራራውን ከከበበው ኃይል ድንገተኛ ጥቃት ሊደርስብን ይችላል፡፡"

ጌራና ኪራኮስም ወደ ዜና ማርያም ተረተሮች አማተሩ፡፡ ከዜና ማርያም ተረተር፣ በቅቤን ባህር፣ በታች በሰብር ባህር፣ ተሻግሮ የኪብራ ወንዝ ሸለቆ፣ ከዛም ጣቅርን፡፡

"እንሞክረው!" አለ ጌራ ተራሮቹን ሲያማትር ከቆየ በኋላ፡፡ "እንሞክር! 'ከሞከርነው ነገር ይልቅ ያልሞከርነው ነው 'ሚቆጨኝ' ብሏል ታላቁ ገጣሚ ፀጋዬ ገብረ መድህን፡፡" ጌራ እንሞክር የሚል ቃል ካመጣ ይህችን አባባል ሳይል ማለፍ

አይችልም፡፡ በአባባሷ የተሰላቸ ሰው አይቶ ስለማያውቅ ይሆናል፤ ሲደጋገማት አይሸማቀቅም፡፡ "ደግሞም መለዮአችን ተራራውን የከበበው ሠራዊት ዓይነት በመሆኑ ባላገሮቹ ተመሳሳይ ሰራዊት እየተጨመረ እንጂ ሌላ ኃይል መሆኑን ስለማይገምቱ ጥርጣሬ አያድርባቸውም፡፡" ጌራ የዴር33ን መሪ የሚጨብጥበት ጊዜ ራቀው፡፡

"የከበባቸው ኃይል ደምስሶአቸው ወደ ተራራው ገብቶ ይሆን?... ለምን ተኩሱ ቆመ?" ኪራኮስ የስጋት መንፈስ ወረረው፡፡

"በአንዴ ሙከራማ ሊገባ አይችልም፡፡ ምናልባት ርሀቡ እያደከማቸው ሲመጣ ሊገባ ይችላል፡፡ ሚራዥ እንዲህ በቀላሉ የሚበገር ሰው አይደለም፡፡" ኮ/ል አሊጋዝ ይህን ካሉ በኋላ "እንቀሳቀስ!" የሚል ትዕዛዝ አስተላለፉ፡፡

# ፴፫

ነጭ ባንዲራ እያውለበለበ ሽቅብ ተራራውን የሚወጣው ሰውዬ እየቀረበ መጣ፡፡ ጉሙን ለመበተን የሚወነጨፈው ኃይለኛ ነፋስ ነጯን ባንዲራ ከእጁ ሊመነጭቅ ይታገላል፡፡ ሚራዥ የሩቅ አቅርብ መነጽሩን ሰውዬው ላይ ተክሎ በማጤን ላይ ነው፡፡ ነፋሱ ኮቱን ግራና ቀኝ እንደ መጋረጃ ከፍት አርጎ ድርግም ሲያደርገው አንድ ነገር የተመለከተ መሰለው፡፡

"ዣንጊዳ!" አለ ያየውን ማመን አቅቶት፡፡ "ሰውዬው ፈንጂ ታጥቋል፡፡ አጥፍቶ ሊጠፋ ወይም ምሽግ አፍርስ ተብሎ የተላከ መሆን አለበት፡፡ እነዚህ እርጉሞች በነጭ ባንዲራ ኃጢአት ቢሰሩ አይደንቅም፡፡"

ባለነጩ ባንዲራ ፍጥነቱን ጨመረ፡፡ ሚራዥ ልዩ 'ሳቅ በሳቅ' ሽጉጡን ከወገቡ ላጥ አርጎ

"ባለህበት ቁም!" ሲል ጮኸ፡፡

"እንዳትመታው!" አለ ዣንጊዳ ሩቅ አቅርብ መነጽሩን ተቀብሎ የባለ ነጩን ባንዲራ ወገብ እየተመለከተ፡፡ ወገቡ በተቀጣጣይ ፈንጂ ዘሟል፡፡ "ዓለም አቀፍ ህግን ጥሰን ስህተት በመስራት ልንተባበራቸው አይገባም፡፡ ይህን ስህተት ብንሰራ ለእኛ የሚፋለሙት ሰዎቻችን ሳይቀር በእኛ ላይ ያላቸው እምነት ይሸረሸራል፡፡ እነሱም ይህንኑ ነው የፈለጉት፡፡"

ሰውዬው ባለበት እንደህውልት ቆመ፡፡ ረጂም ነው፡፡

"እዛው ሆነህ ተናገር! መልዕክትህ ይሰማናል!" ሲል ጮኸ ሚራዥ፡፡

"ወታደራዊ ምስጢር በመሆኑ ሁሉም እየሰማኝ ጮሄ አልናገርም፡፡ ሚራዥ ለሚባል ሰው ካልሆነ በቀር ለማንም የያዝኩትን መልዕክት እንዳላደርስ ታዝዣለሁ፡፡" ሲል ባለነጩ ባንዲራ ሰውዬ የሚያፏጨውን ነፋስ እየታገለ ተናገረ፡፡

"ትጥቅህን ካለህበት አስር ሜትር ወደ ኋላ አፈግፍገህ ካልፈታህ በቀር ማንንም ማናገር አትችልም!" አለው ሚራዥ በሽጉጡ ወደኋላው እያመለከተው።

"እንዲያውም ከዚህ በላይ ከሚራዥ ጋር ካልሆነ በቀር አልነጋገርም። ነጭ ባንዲራ ይገፍ ልትመታኝ ትፈልጋለህ? ሚራዥ ይህን አይነት ብልግና በደንብ አስጠንቶህል ማለት ነው? ይህ ውርደት ነው! ቅሌት ነው!"

"ቅሌትስ ታጥቆ ነጭ ባንዲራ መያዝ ነው። ትጥቅህን ፍታ! አለበለዚያ ጥቁር ባንዲራ ይዘህ መምጣት ነበረብህ!"

"አልታጠኩም ከተፈለገ ሚራዥ መጥቶ ሊፈትሸኝ ይችላል።"

ሚራዥና ዣንጊዳ እርስ በእርስ ተያዩ። ሰውዬው ሚራዥን ለመበታተን እንደተላከ ሁለቱም ድርሰውበታል። ያለ ንግግር ተግባቡ።

"ነጩን ባዲራ ጣለውና መጥቼ ትጥቅህን እስፈታሀለሁ" አለ ሚራዥ ለውሳኔ ተቸግሮ። "ወይ ነጩን ባዲራ ጣል፣ ወይ ትጥቅህን ፍታ። አለበለዚያ ባለህበት ቁመህ መዋል ትችላለህ።"

"ለመሆኑ አንተ ነህ ሚራዥ?!"

"አዎ እኔ ነኝ ሚራዥ"

"የሰማይ ስባሪ የምታህል ይመስለኝ ነበር።" ሰውየው ከትከት ብሎ ሳቀ። "ለመሆኑ ለምንድን ነው ሰዎችህን በረሃብ የምትቀጣቸው? ይህ ጀብደኝነትህ ሰው እያስፈጀና እየፈጀ መሆኑን ተገንዝበሽዋል?!" ሰውዬው እየቀረበ መጣ። ከቆመበት አንድ ሜትር እንደ ቀረበ ሚራዥ አንባረቀበት።

ይባስ ፍጥነቱን ጨመረ። "ተቃቅፈን እንሞታለን!" ብሎ ወደ ሚራዥ ሲምዘገዘግ የመትረዬስ ጥይት ላዩ ላይ ዘነበበት። በስተምዕራብ በኩል ከዞረ የመትረዬስ አፍ። ከሲጻራ መትረዬስ አፎት። ከፍተኛ ፍንዳታ ተፈጠረ። ከምሽጉ በታች ያለው ቦታ ተበተራረፈ። የፈንጁ ፍንጥርጣሪ ምሽጉ ድረስ እተወረወረ ፎገሰው። አካባቢው በጭስ ታፈነ።

# ፴፮

የጣቅርን ሰማይ መጥቆር ጀምሯል፡፡ የዙንዝ ሸለቆ ጥላ ወድቆበታል፡፡ ጀንበሯ ምድሩን በመሰናበት ላይ ናት፡፡ በኮ/ል አሊ.ጋዝ የሚመራው ቡድን ከማንቶገራ ሸለቆ ተነስቶ ሲሹሎከሎክ ከዋለ በኋላ የፀሐይዋን መጥለቅ ተከትሎ ከተራራው በስተምዕራብ ከሚገኘው የኪብራ ወንዝ ሸለቆ ውስጥ ያላንዳች ኮሽታ ቢገባም፣ በዚህ በኩል አድፍጦ ተራራውን ይጠብቅ ከነበረ ኃይል ጋር ተፋጠጠ፡፡ ኮ/ል አሊ.ጋዝ ድንገተኛ ጥቃት ከመሰንዘር በቀር ሌላ አማራጭ እንደሌለ ተገነዘቡ፡፡

ከኋላው ጥቃት የተሰነዘረበት ኃይል ቀፎው እንደተነካ ንብ ይርመሰመስ ጀመር፡፡ ተመሳሳይ መለዮ ከለበሰና አንድ አይነት ትጥቅ ከታጠቀ ኃይል የተቃጣበት ጥቃት ለረጂም ደቂቃዎች አተረማመሰው፡፡ ወታደራዊ ራዲዮኖች ከወዲያ ወዲህ ይንጫጩ ጀመር፡፡ ገሚሱ ጠላቱን መለየት አቅቶት እርስ በእርሱ ይጠዛጠዝ ገባ፡፡

ኪራኮስና ጌራ ድንገተኛው ተኩስ ባስከፈተው ጥቂት ቀዳዳ ሾልከው ወደ ተራራው እንዲወጡ ከኮ/ል አሊ.ጋዝ ትዕዛዝ እንደደረሳቸው ተራራውን ተያያዙት፡፡ ኮ/ል አሊ.ጋዝ የማረኩትን መትረዬስ ይዘው ሽፋን በመስጠት የርሳቸው ኃይል ሰብሮ በማለፍ እነ ጌራን እንዲከላከል ትዕዛዝ ሰጡ፡፡

ፙ ፙ ፙ

ሚራኘር በስተምዕራብ የሚደረገው ፍልሚያ ቅጡ ሊገባው አልቻለም፡፡ በዚሁ አፍታ በስተምሥራቅ አንድ ሌላ ነጭ ባንዲራ የሚያውለበልብ ሰው ተራራውን ሲወጣ ተመለከተ፡፡ ድምፅ ማጉያ ይዟል፡፡

"ሚራዥ! ይሰማሀል?!....ሚራዥ..." በሚንኮራኮረው ድምጽ ማጉያ ሚራዥን ይጣራ ጀመር ተራራውን እንዲጋመስ፡፡ ሚራዥ አፀፋውን በዝምት መለሰ፡፡ ነጭ ባንዲራ ያገር ያሰለቸው ይመስላል፡፡ ሰውዬው ግን እያዳመጠው እንደሆነ በመገመት ንግግሩን በድምጽ ማጉያው ቀጠለ፡፡

"ሚራዥ! አዳምጠኝ፡፡ ከዚህ ጦርነት ሁለታችንም የምናተርፈው እልቂት ብቻ ነው፡፡ በኛ በኩል በተደረሰ ስምምነት መሠረት ተራራውን ከከበበው ኃይል በአንድ በኩል ያለው ሠራዊት ተነስቶላችሁ ተራራውን ለቃችሁ እንድትወጡ ወስነናል፡፡ ሚራዥ ይህን ዕድል አለመጠቀም ጭኝነት ነው፤ ጅልነትም ጭምር፡፡ ይህ ያንተ ውሳኔ የሚያሻው ጉዳይ ነው፡፡ ... ወገኖችህን በከንቱ አታስጨርሳቸው፡፡ ተራራው..." ድምጽ ማጉያው ሲነፋነፍበት አመድ እንዳጠለቀው እጅ እፍ እፍ ብሎ ቀጠለ፡፡ "ተራራው በደም ከመታጠቡ በፊት አስብበት፡፡ እንደራባችሁ እናውቃለን፡፡ ከተራራው በታች በተዘጋጀላችሁ ድንኳን ውስጥ የሚበላም የሚጠጣም ቀርቦ እየጠበቃችሁ ነው፡፡ ሚራዥ ... ለሰብአዊነት ክብር ትሠጣለህ የሚል ግምት ነበረን፡፡ መልስህን ሳላገኝ እንዳልመለስ፣ ትዕዛዝ ተሰጥቶኛል፡፡ ዝም አትበል፡፡ ይህ እድል ተመልሶ አይሰጥህም፡፡"

ሚራዥ በበኩሉ የድምጽ ማጉያ አስመጥቶ ምላሽ ከመስጠቱ በፊት ከእርሱ ሰዎች ጋር ተመካከረ፡፡ ሳዶፍ በድምጽ ማጉያው የሰማው ነገር አስቆጣል
ምሽጋችንን አስለቅቀው ሲያበቁ እንደ ድፎ ዳቦ ከላይም ከታችም ሊያነዱብን በማቀዳቸው እንጂ ሌላ አስበው አይደለም፡፡" ሲል ተናገረ፡፡

"አሁንም ቢሆን በዚህ አዘናግተው ሊወጉን እንዳሰቡ ግልጽ ነው፡፡" ገርንጊዳ አከለ፡፡

ከነዚህና ከሌሎች የሀሳብ ልውውጦች በኋላ ሚራዥ በድምጽ ማጉያው ምላሽ መስጠት ጀመረ፡፡ ድምጹን ዘለግ አድርጎ፡፡ ማጉያው ምላሽ መስጠት ጀመረ፡፡ ድምጹን ዘለግ አድርጎ፡፡ በስተምዕራብ የሚሰማው የተኩስ ልውውጥ ብዙ ጆሮዎችን ባይቆነጥጥ ኖሮ በተራራው ዙሪያ የከበበው ኃይል ሁሉ ይሰማው ነበር፡፡

"ስለ ቸርነታችሁ እናመሰግናለን፡፡" ሲል ነበር መልስ መስጠት የጀመረው፡፡ "እናንተ በከፈታችሁልን መንገድ ሳይሆን እኛ በምንጠርገው መንገድ ለመሄድ አቅሙም ብቃቱም እንዳለን በቅርቡ ታረጋግጣላችሁ፡፡ ክቡር መልእክተኛ ትሰማኝ ከሆነ ለአክሎግ እንዲህ ብለህ ንገረው፡፡ ርቦህ ከሆነ ግዴለህም ነጭ ባንዲራ ይዘህ መጥተህ እስክትጠግብ በልተህ መመለስ ትችለህ በለው፡፡ እንኳንስ ለእኛ ለናንተ የሚተርፍ ምግብ ሞልቶናል፡፡ ደግሞም በሆዱ የሚደለል እንደ አክሎግ እና እንደ አያና ያለ ሰው ካልሆነ በቀር ይህን ያላዋቂዎች ሀሳብ የሚያመጣ አይገኝም፡፡ እኛ ከሆድ ያለፈ ዓላማ፣ ከዳቦ የዘለለ ህልም ያለን ሰዎች እንደሆንን አክሎግ አሳምሮ ያውቀዋል፡፡ በአፋጣኝ ተራራውን ለቃችሁ ካልተመለሳችሁ ከፍተኛ እልቂት እንደሚጠብቃችሁ ሂድና ተናገር፡፡" ሚራዥ ትንፋሽ ወሰዶ አቅም ሊያሳጣው የታገለውን ርሀብ ለመታገል ያህል፡፡

"ተራራውን ያስከበባችሁትን ኃይል ዋሽታችሁታል ማለት ነው፡፡ ከማን ጋር እንደሚፋለም እንኳ አልነገራችሁትም፡፡ ለዚህ ውሸታችሁ ደግሞ ተጋቢውን ቅጣት ታገኛላችሁ፡፡ ችግሩን መፍታት የሚቻለው አንድ ነገር በማድረግ ብቻ ነው፡፡ እሱም ዋሽታችሁ ተራራውን ያስከበባችሁትን ኃይል እውነቱን በመናገር ወደመጣበት መመለስ ነው፡፡"

"ሚራዥ.... አንድ ጊዜ ብቻ አዳምጠኝ፡፡ ከዚህ በኋላ ይህ እድል አይሰጥህም፡፡ አንድ ምክር ብቻ ተቀበል፡፡ .... አታስጨርሳቸው!" መልእክተኛው ቁልቁል ተንደረደረ፡፡

በዚሁ ቅጽበት ከፍተኛ የተኩስ ድምጽ ተሰማ፡፡ ከነ ሚራዥ ምሽግ ላይ የላውንቸር አረር ይራገፍ ጀመር፡፡ ሚራዥ እንደገመተውም እያዘናጓቸው ነበር፡፡ ወደ ተራራው ወገብም ከፍተኛ ቁጥር ያለው ኃይል እየተርመሰመሰ በመውጣት ላይ ነበር፡፡ ከወዲህም የአፀፋ ተኩስ ተጀመረ፡፡

❋ ❋ ❋

ከተራራው በስተምዕራብ ከበባውን ሰብሮ ለመግባት የሞከረው የነኮ/ል አሊጋዝ ኃይል ከፍተኛ እልቂት ደርሶበታል፡፡ ምንም እንኳ ከነርሱም የተሰነዘረው ጥቃት የማይናቅ ቢሆንም

በሕይወት መትረፍና ወደ ተራራው መውጣት የቻሉት ስድስት ሰዎች ብቻ ነበሩ፡፡ ኮ/ል አሊጋዝ፣ ጌራ፣ ኪራኮስና ሌላ ሶስት ሰዎች፡፡

አሁንም ቢሆን ተኩሱ አልቆመም፡፡ ከታች ተራራውን የሚወጡ ሰዎችን ለማስቀረት የሚያፏጩ ጥይቶችን ይልካሉ፤ የዛፎች ቅርንጫፎች ይቀነጥሳሉ፣ ድንጋዮች ወደ አመድነት ይለወጣሉ፤ ፍንጥቅጣቂዎች ተራራውን ያርሳሉ፡፡ ከላይ ወደታች ደግሞ የኮ/ል አሊጋዝ መትረዬስ ያሽካካል የነጌራ የነፍስ ወከፍ መሳሪያ ይንተገተጋል፡፡

በዚህ መሀል ጌራ፣ ኪራኮስ አቃስቶ ሲወድቅ ተመለከተው፡፡ በደመነፍስ ተወርውሮ ሲደርስ ክፉኛ ተመትቶ ነበር፡፡ በቅጽበት የወደቀበትን መሬት የደም ጎርፍ ሲያጠልቀው ተመለከተ፡፡ ኮ/ል አሊጋዝ የኪራኮስን መውደቅ ቢመለከቱም የሽፍን ተኩሳቸውን ማቆም አልቻሉም፡፡ ጌራ መለዮውን አውልቆ የኪራኮስን የደም ጎርፍ ለማስቆም ግጥም አድርጎ አሰረለት፡፡ ወዲያውም ተሸከመውና ተራራውን እያማጠ ለመውጣት ሞከረ፡፡ ኮ/ል አሊጋዝና ሦስቱ ሰዎቻቸው ከኋላ ሽፋን እየሰጡ ተከተሉት፡፡

፠ ፠ ፠

ከተራራው በስተምሥራቅ ያለው ኃይል የመጨረሻ አቅሙን አጠራቅሞ ለድምሰሳ ተራራውን እንደ ሸረሪት በፍጥነት መውጣት ቀጥሏል፡፡

ሳዶና እያነጣጠረ ይለቅመው ገባ፡፡ ገቢንጊዳ የአንዱን የተሰዋ ሰው መትረዬስ ይዞ ከበታች የሚመጣውን ኃይል መጥረግ ጀምሯል፡፡ ማርዬ ዋቆ ማርዬ ከአድያም የሚማገድለትን ፍም ቁልቁል ይለቀው ይዟል፡፡ አንጎታ በእርሷ በኩል ምሽጉን ለመያዝ የሚጣደፈውን ኃይል ለመግታት በመሞከር ላይ ናት፡፡

በዚህ መሀል የሲጳራ መትረዬስ አሳት መትፋት ማቆሙን የተገነዘበው ሚራኸ ወደ ዛው ተምዘገዘገ፡፡ ወደ ምሽጉ ሲገባ ያየውን ማመን አልቻለም፡፡ የሲጳራ ረዳት እንዳልሆነ ሆኖ ወድቋል፡፡ እርሷም በደም ተነክራ ተንጋላለች፡፡ በዚህ ቅጽበት

ገርንጊዳ መትረዬሱን ለሌላ ተኳሽ ሰጥቶ ወደ ሲጻራ ምሽግ እየተሹለከለከ ሲገባ ሚራዥ ደንዝዞ ደረሰ፡፡ ሲጻራ ተመትታለች፡፡ ሚራዥ አንዳች ነገር ሲወረውና ሲጨልምበት ተሰማው፡፡ … ገርንጊዳ ሲጻራን አፋፍሶ አስተካከላት፡፡ በዚሁ አፍታ አንድ አዲስ ድምጽ ሰማ፡፡ የህጻን ልጅ ለቅሶ፡፡ … በደም ከተነከረ ቀሚሷ ውስጥ፡፡

"ህጻኑን! ህጻኑን! ሚራዥ ፍጠን! ህጻኑን!" ገርንጊዳ ጮኸ፡፡ ሚራዥ ግን አንዱንም ማድረግ አልቻለም፡፡ ደንግዟል፡፡ ገርንጊዳ ወደ ህጻኑ እጁን ሰደደ፡፡

# ፴፯

አክሎግ ተራራው ላይ የተፋፋመውን ጦርነት ሸቅብ ተመለከተ፡፡ አያናም የእርሱን ዓይን ተከትሎ አሻቅቦ ካዬ በኋላ ሰዓቱን ተመለከተ፤

...2፡10...

"ሰዓቱ ደርሷል፡፡"

"ሮበርት ጋሎም ደርሷል፡፡" አክሎግ ሲጋራውን አቀጣጥሎ ሁለቴ ካቦለለ በኋላ ከተራራው ላይ ዓይኖቹን ሳይነቅል መለሰለት፡፡ "አሁን ደውሎልኝ ነበር፡፡"

"ለአንተ ብቻ ለምን እንደሚደውል አይገባኝም፡፡" አለ አያናም የራሱን ሲጋራ እያቀጣጠለ፡፡

አክሎግ አልመለሰለትም፡፡

"እንፍጠና ታዲያ!......" እያና ወደ አዲስ ዘመን ቶሎ ሄደው የኢንጂነሩን ሽያጭ ለማከናወን ተጣድፏል፡፡ "ጦርነቱ ከመጠናቀቁ በፊት ሁሉ ነገር መጠናቀቅ አለበት፡፡ በዛ ላይ ቀንጠፋው እዛው ነው፡፡"

"አያና.....አትቸኩል፡፡ ለኛ ያለውን እንጀራ ይሸበርራል እንጂ ማንም አይበላውም፡፡"

"ሆነም ቀረም መሰቡን ከድኖ መጠበቅ የኛ ፋንታ ነው፡፡"

ጉዟቸውን ጀመሩ..... ወደ አዲስ ዘመን፡፡

ለአርባ ደቂቃዎች ያህል ከተጓዙ በኋላ አክሎግ ርምጃውን ገትቶ ወደ አያና ተመለከተ፡፡

"ትጠራጠረኛለህ ልበል?!፡፡" አክሎግ የአያናን ዓይኖች ፈለገ፣ በሲጋራው ጫፍ ወጋገን ውስጥ፡፡ ጢሱን አትጎልጉሎ የራሱን ፊት ሸፈነ፡፡ ከዛም ፈገግ አለ፡፡ "አያና.... እኔን መጠራጠር ነበረብህ ብዬ አላስብም፡፡ ....አዝናለሁ፡፡ በእርግጥ

ገንዘብ ክፉ ነው፡፡ ...ያለፈውን ቀብድ ከቀንጠፋው ጋር የየድርሻችን ተካፍለናል፡፡ እሱንም ቢሆን ልንጠረጥረው አይገባም፡፡ ተራራው ውስጥ እያለን እንኳ የየድርሻችን አልነሳንም፡፡ እንዲያውም እሱ ነገሩን ቢጨርሰው ይሻላል፡፡" አለ አክሎግ የኢያናን ፊት አሁንም እያጠና፡፡ "እኛ እዚህ ያለውን ጦርነት ጨርሰን ብንሄድ ይሻላል፡፡ ምንም የሚያስቸኩል ነገር የለም፡፡" አክሎግ ፊቱን አዙሮ ወደ ተራራው ተመለከተ፡፡ "የኛዎቹ ከምሽት ለመድረስ የቀራቸው ጥቂት ነው፡፡" ሲል እንደዘረ ተናገረ፡፡

"እንዲህማ ሊሆን አይገባም፡፡ እኛ ከዚህ ምን እንሠራለን? ተገቢውን ትዕዛዝና መረጃ ሰጥተናል፡፡ የኢንጂነሩን ጉዳይ ጨርሰን እስክንመለስም ጦርነቱ የሚያበቃ አይመስለኝም፡፡ ለምን ይህን ጉዳይ ችላ ትላለህ?! የቀንጠፋውን ስልክ ቅድም ሞክሬ ነበር፡፡ ዝግ ነው፡፡ ይህ ጉዳይ ከፍተኛ ጥንቃቄ የሚጠይቅ ነው፡፡ ዞሮ ዞሮ ሰው እየሸጥን ነው፡፡" ኢያና ይህን ብሎ ዝም አለ፡፡

"ምን አልክ!? ሰው እየሸጥን ነው!?" አክሎግ ለማጉረጥረጥ ሞከረና መልሶ ፈገግ አለ፡፡ "ሰብአዊ ነኝ ለማለት ፈልገህ ነው!? ከመቼ ወዲህ?...... ከመቼ ወዲህ ነው ኢያና? አ... አዝናለሁ፡፡"

"ምኔ ነው የሚያሳዝንህ?"

በዚህ ቅጽበት ኢያና ያየውን ማመን አልቻለም፡፡ የአክሎግ ማፈኛ የተገጠመለት ሽጉጥ፣ ድምጽ አልባውን ሞት ሊለቅበት ተዘጋጅቶ ነበር፡፡ ወደኋላ ለማፈግፈግ ሞከረ፣ አልቻለም፡፡ እጁን በደመነፍስ ወደ ሽንጡ ከመላኩ በፊት፣ አንገቱን በስቶ፣ ጉሮሮውን በጥሳ አንዲት ጥይት ያለፈችው፣ ወዲያው ነበር- የሽጉጡን አፎት ከማየቱ፡፡

ኢያና አንገቱን እንደከዘራ አጥፎ ወደቀ፡፡ አክሎግ ቁልቁል ኢያናን እየተመለከተ ፈገግ አለ፡፡ "አንዳንድ ሀብቶችን ለሰብሰብ መካፈል ፍትሀዊ አይደለም፡፡ አንደኛው በደንብ መጥገብ አለበት፡፡ ሀበሻ በባህሪው ከአንድ ድስት ስድስት እጅ መከተት ልማዱ ነው፡፡ ይህ ክፉ አመል እስካሁን እንዳይጠግብ አድርጎታል፡፡ ወደ አንዱ ድስት የሚሰደዱ ብዙ እጆች ማንንም አያጠግቡም፡፡ ወደ ድስቱ የሚገቡ እጆች መቀነስ አለባቸው፡፡

ድህነትን ለመቀነስ እጆችን መቀነስ እንደ አጀንዳ መያዝ ያለበት ጉዳይ ነው፡፡" እንደገና በምፀት ፈገግ ብሎ ልቡ ላይ ደገመው፡፡

አክሎግ አያናን እስከ ወዲያኛው መሸኘቱን ካረጋገጠ በኋላ መሬት ለመሬት እንዳጎዛ እየጎተተ ወስዶ ቁልቁል ወደሚወርደው የሸኒ ወንዝ ጨመረው፡፡

"ደህና ሁን አያና!...አንተ ብልጣ ሞኝ!....." የአያናን ጉዞ ጥቂት ቆሞ እያጨሰ ከተመለከተ በኋላ ወደ አዲስ ዘመን መንዙን ትቶ ወደ ተራራው መመለስ ጀመረ፡፡ የጥይቱ ፉጨት እስካሁን አልቆመም፡፡

# ፴፰

አክሎግ ከተራራው ስር ወደ ሚገኘው ጊዜያዊ ማዘገር ጣቢያ እንደደረሰ ሽቅብ ወደ ተራራው ተመለከተ፡፡ ነጭ ባንዲራ ይዞ ቁልቁል የሚንደረደር ሰው አዬ፡፡ የሆነ ነገር ታቅፏል፡፡

እየቀረበ ሲመጣ የታቀፈው ነገር ህጻን ልጅ እንደሆነ ተገነዘበ፡፡ የጨረቃዋ ብርሃን ይህ ቁልቁል የሚንደረደር ሰው ገርንጊዳ መሆኑን አስለየው፡፡ ይጣደፋል፡፡ ሁለት ጊዜ ያህል የረገጠው ድንጋይ ተገልብጦ ሊጥለው ተፍገምግሞ ሲተርፍ አስተውሏል፡፡

"ቁም!" አለው አክሎግ ገርንጊዳ አስራ አምስት ሜትር ያህል እንደቀረበ፡፡ ገርንጊዳም ድምጹ የአክሎግ መሆኑን ወዲያው አወቀ፡፡

"አክሎግ.... አባክህ... አሳልፈኝ፡፡" ሲል ተማፀነ ገርንጊዳ፡፡ "ይህ ህጻን በሞትና በሕይወት መካከል ይገኛል፡፡ የምታጠባ ሴት ፍለጋ ወደ መንደሩ በመውረድ ላይ ነኝ፡፡"

"እው!.... ሲጻራ ወለደች?! .... ሃሃሃ.... የሚራኸር ልጅ....ሃሃሃ..." አክሎግ ተሳለቀ፡፡ 'ሲጻራ ሞታለች!' ሲል አሰበ፡ 'አንድ ማፍዮድ ተቆረጠ!'

"ህጻኑ ያለው ጊዜ አጭር ነው አባክህ .... ተ... ተለመነኝ፡፡ ስለ..."

"ነጩን ባንዲራም ... ህጻኑንም አስቀምጠህ ቁም!" አክሎግ ሽጉጡን አቀባበለ፡፡

"አክሎግ!... ነውር ነው!...ነ... ነጭ ባንዲራ ይዤ ልትመታኝ?! ይህማ ..."

"እሱን የእናንተ ልጅ አስቀምጥ ብየሃለሁ! ይልቅስ ራስህ በነጩ ባንዲራ አትቀልድ! እንኳን ልጁ አባቱም ለዚህች ሀገር አልጠቀመም፡፡ ጣለው!"

"ይህን ጭካኔ ከወዴት ወረስከው አክሎግ?.... እኔ መሳሪያ አልያዝኩም፡፡ ባዶ እጄን ነኝ፡፡ መሳሪያዬ ይህ ነጭ

ባንዲራ ብቻ ነው፡፡ እኔን ተኩስና ግደለኝ፡፡ ይህ ህጻን ግን ገና በማንም ያላደፈ እንደዚህ ባንዲራ የጠራ አዕምሮ ይዞ የመጣ ሰው ነው፡፡ ገና በማንም ቀለም ያልቀለመ፣ በማንም እድፍ ያላደፈ ህሊናህ የወደደውን አድርግ እንጂ ልጁንም ባንዲራውንም አልጥልም፡፡"

"ጣለው ብየሃለሁ! እቆጥራለሁ! ሦስት!..."

"ይህን እንኳንስ የዓለማቀፍ የጦርነት ሥነ-ምግባር ህግ ተፈኤምሮበት ኢትዮጵያዊ ሥነ-ምግባር እንኳን አይፈቅድልህም፡፡"

"ሁለት!..."

ከአክሎግ ኋላ አንድ ሰው ተጠጋ፡፡ የሻለቃ ማዕረግ ያለው ወታደር፡፡ "አክሎግ! ይህ መሆን የሌለበት ጉዳይ ነው፡፡ የዚህ ጦር አዛዥ እኔ ነኝ፡፡ ይህን አፀያፊ ተግባር እፊቴ እንድትፈጽም አልፈቅድልህም፡፡ ሽጉጥህን ወደ ወገብህ መልስ፡፡"

"ወታደርህን እዘዝ እንጂ ታዲያ እኔን ማን አዛዥ አደረገህ!..."

"ቢሆንም እዚህ ይህን እድታደርግ አልፈቅድልህም፡፡...እለፍ!" ሲል አዛገቡ ሎሆ ለዣንጊዳ የእጅ ምልክት ሰጠው፡፡ "የመንደር ውሻ እንዳይነክስህ ሁለት ወታደሮች ያጅቡሀል፡፡"

"ፈጣሪ ውለታውን ይክፈልልኝ ጌታዬ!...." ዣንጊዳ ሻለቃውን አመስግኖ ወደ መንደሩ ተፈተለከ፡፡ ሁለት የታዘዙ ወታደሮችም ከኋላው ተከተሉት፡፡ ቆየት ብሎም የውሻ ጩኸት መንደሩን ያቀልጠው ጀመር፡፡

⁂ ⁂ ⁂

የተራራው የህክምና ቡድን ቁስለኞቹት ለማዳን በመተራመስ ላይ ነው፡፡ ኪራኮስና ሲጳራ የሚተርፉ አይመስሉም፡፡

ኮ/ል አሊጋገዝና ጌራ ኪራኮስን ይዘው በቃላት ልውውጥ የተራራውን ወገኖቻቸውን ተቀላቅለው ኪራኮስን ለህክምና ቡድኑ ካስረከቡ በኋላ በሶስት የሀሳብ አውታር ተወጥረዋል፡፡ አንደኛው የተራራውን ፍልሚያ መቀላቀል ሲሆን፣ ሁለተኛው ደግሞ

ዴር33ን በማስነሳት አዲስ ዘመን ውስጥ የተያዙትን ሻጊዝንና ሜሮዳን ማትረፍ ነው፡፡ በተለይም የሻጊዝ ጉዳይ ጊዜ የሚሰጥ እንዳልሆነ ተማምነዋል፡፡ ለሸያጭ ከመቅረቡም በላይ ሁለቱም የታሰሩበትን ቦታ ካርታ ሰርቶ በማንቶገራ ሸለቆ እያለ ያቀበላቸው አባል አሁንም እዛው ሆኖ ባደረሳቸው መረጃ መሰረት፣ ሮበርት ጋሎ የሚባለው የሲ.አይ.ኤ. ወኪል አዲስ ዘመን ደርሷል፡፡ ሌላኛውና ዋነኛው ጉዳይ ሆኖ ያገኙት የዋሻ ውስጥ መንገዱን በኪራኮስ አባት ማስታወሻ ቁልፍ በመክፈት ወገኖቻቸውን ማስመለጥ ነው፡፡

ስለዚህ ጉዳይ ለሚራዥ ለማስረዳት እንኳ ጊዜ አላገኙም፡፡ ሚራዥ ሲጻራን የህክምና ቡድኑ ከወሰዳት በኋላ ወደ ፍልሚያው እንዲመለስ ተገዷል፡፡ በመሆኑም፣ የሲጻራን መትረዬስ ይዞ በዛው በኩል በተፈጠረው ክፍተት ምክንያት ከፉኛ በመጠጋት ላይ ከነበረ ኃይል ጋር መተጋተጉን ቀጥሏል፡፡

⁂ ⁂ ⁂

አክሎማ ከሮበርት ጋሎ የስልክ ጥሪ ከደረሰው በኋላ ወደ አዲስ ዘመን መፈትለክ ጀምሯል፡፡የሸኒን ወንዝ ለመሻገር የወሰደበትን ጊዜ አያስታውሰውም፡፡ በደመነፍስ እያለከለከ በመሮጥ ላይ ነው፡፡

⁂ ⁂ ⁂

አዲስ ዘመን፡፡ በጥብቅ በሚጠበቀው መኖሪያ ቤት ውስጥ ቀንጠፋውና ሮበርት ጋሎ ውስኪ በመጎንጨት ላይ ናቸው፡፡

"እየመጣ ነው፡፡" አለ ቀንጠፋው ወደ አክሎማ ደውሎ ከተነጋገረ በኋላ፡፡ "በጥቂት ደቂቃዎች ውስጥ ይደርሳል፡፡"

⁂ ⁂ ⁂

"ቅድሚያ ለሚሰጠው ቅድሚያ መስጠት ተገቢ ነው፡፡ 'አሥር ያባረረ አንድ አይዝም' እንደሚባለው መሆን የለብንም፡፡"

"ኮ/ል ... እስኪ እርስዎ ቅደሚያ የሚሰጠውን ጉዳይ ይንገሩኝ፡፡" አለ ጌራ ረጂሙን ኮሪደር እያቋረጡ እያሉ፡፡

"መጀመሪያ ዴር33ን አሳነሳ፡፡ ከዛ ቀጥሎ ማዘዙን ለእኔ ተወው፡፡"

ጌራ የዴር33ን ሞተር በፍጥነት ቆሰቆሰ፡፡ ባለ ሃምሳ ካሊበር መትረዬስ ከበቂ ጥይት ጋር ገብቶ ተወደረ፡፡ የእጅ ቦንቦች ሆድዋን ወጠቁት፡፡ አራት ከማንደዶች ገብተው ቦታ ቦታቸውን ያዙ፡፡ ኮ/ሉ ከጌራ ጎን ተሰየሙ፡፡

ከጥቂት ደቂቃዎች በኋላ አንድ ሐዬልሲ የመሰለ ብረት ከተራራው ሆድ ተመንጥቆ ሲወጣ ታዬ፡፡ በተራራው ላይም ከተራራው በታችም ያሉ ዓይኖች ሁሉ ወደ ሰማይ ተተኮሱ፡፡ አንገቶች ወደ ኋላ ታጠፉ፡፡ በጣቅርን ሰማይ ላይ የሚገለባበጠው የብረት ንስር ተራራውን ሁለቴ ከዞረ በኋላ ዝቅ ብሎ እሳት መትፋት ጀመረ፡፡ ፍም፡፡ የተጠመደው መትረዬስ የእሳት ጠበል ይረጭ ጀመር፡፡

ሚራዥር ቀና ብሎ ወደ ሰማይ ተመለከተ፡፡ ጌራ በጥጉ ሁለቴ በዴር33 ተገለባብጦ ሲያልፍ አንዳች ነገር ወረረው፡፡

"አጥቁ!" ሲል መልእክት አስተላለፈ- ሚራዥር፡፡ "አጥቁ! አጥቁ!..." ምሽጉ ገነፈለ፡፡

የሚያስቀውን መሣሪያ እስካሁን አልፎ አልፎ ቢጠቀሙትም በገፍ ጥቅም ላይ የዋለው ግን አሁን ነው፡፡ ልዩ ስልጠና የተሰጣቸው ልዩ ኃይሎች እስካሁን በመከላከሉ ፍልሚያ ላይ እንዳይሳተፉ ተደርገዋል፡፡ በሚራዥር እቅድ መሠረት እነዚህን በውድ ወጪ የሰለጠኑ ኃይሎች አላግባብ መጠቀም ተገቢ አልነበረም፡፡ የነሱ ፋንታ የደረሰውም አሁን እንደሆነ ተገንዝቧል፡፡ እንደሚራዥር አባባል የመከላከል ጦርነት እንደማጥቃት ከባድ ባለመሆኑ ሌሎቹን ማሰለፉ በቂ ነበር፡፡

አሁን ሚራዥርን ጨምሮ ልዩ ኃይሎቹ በሙሉ የታጠቁት 'ሳቅ በሳቅ' የተሰኘውን ልዩ መሣሪያ ነው፡፡ አጠር ብሎ ወፈር ያለ

ቁጥር ዘመናዊ መሣሪያ፡፡ በአፉ ሞትን በሳቅ ለውሶ የሚተፋ ብረት፡፡ ድምፁ የሚች ሳቅ የሆነው ይህ ድምፅ አልባ የጦር ዕቃ፣ የጥይቱ እርሳስ ወደ ሰውነት ከገባ በሁዋላ በደም ውስጥ ገብቶ የሚቀላቀል ቅመም በረቂቅ ቀመር ተዘጋጅቶለታል፡፡ ቀመሩም በምስጢር እንዲያዝ ተደርጓል፡፡ በዱር33 ላይ የተጠመደው ልዩ መትረዬስም ሆነ እንጌራ የታጠቁት ልዩ ሽጉጥ የሳቅ በሳቅን ጥይት የሚጎርስ ሆኖ የተሠራ ነው፡፡ ጠርንቱ ተፋፋመ፡፡

ከተራራው ሥር ያለው አካባቢ ሳቅ በሳቅ ይሆን ጀመር፡፡ አውደ ውጊያው ጦር ሜዳ ሳይሆን ኮቲካላ ቤት መሰለ፡፡ በተራ ጥይት የሚመታው ሲያቃስት የሳቅ በሳቅ ጥይት የገባበት እየተንከተከተ ሲሞት በሚያቃስተው የሚስቅ ይመስል ነበር፡፡

እስከ መሳሪያው ወደ ሰማይ ቱጎ ተበጣጥሶ ወደ ምድር መመለስ፣ ወደ ፊት እንደነበር ተወርውሮ አንገት ላንገት ተናንቆ መፈሳፈስ፣... ትንቅንቁ ቀጠለ፡፡

* * *

ዣንጊዳን የሚያጅቡት ወታደሮች አጥቢ አያፋለጉ ሲወተውቱት ነበር ያመሹት፡፡

“መሣሪያወቻችሁ ከምን ሀገር የተሠሩ ናቸው!”

“አልፈው አልፈው የሚተከሱት ጥይቶቻችሁ አያሳቁ ይገድላሉ!”

“ማነው ያስታጠቃችሁ!?”

“የአርበኞች ማኅበር ናቸው ነው የምትባሉት፡፡ እውነት ነው!”

“አይደለንም! አዛገሮቻችሁን እና አከሎሚ አሳስተዋቸዋል፣ እናንተንም ዋሽተዋችኋል፡፡ ጊዜው ሲደርስ የኛ ማንነት ይገለፅላችኋል፣ ለምን እንደምንፋለምም ያኔ ይገባችኋል፡፡” ለወታደሮቹ አሰልቺ ውትወታ ዣንጊዳ የመለሰላቸው ይህን ብቻ ነበር፡፡

ዣንጊዳ መንደር ለመንደር ህጻኑን ይዞ ሲባዝን አምሽቶ ተስፋ ሊቆርጥ ሲል፣ እንዲት አሮጊት ደረቷን እየደቃች ተቀበለችው፡፡

"እኔ አፈር ልብላ!" ደረቷን እየደቃች ነበር የተቀበለችው፡፡ "እረግ!... እንዴት ነው?... አስተቃቀፋንም ሞታበት ነው? ምጽዕ! እኔ አፈር ልብላ!... እዚህ ማዶ እንዲት አራስ አለች ሲባል ሰምቻለሁ፡፡ ከደረስልን እንሂድ እስቲ!" የአሮጊቷ እርምጃ የሀልም እርምጃ ሆነበት ለገርንጊዳ፡፡ አሮጊቷ ገልታ ገልታ ትል ጀመር፡፡ ታጥፋ መሬት ልትነካ ምንም አልቀራት፡፡ ጎባጣ ናት፡፡ እንኳንስ ልጁን ታቅፋ ልትሄድ ራሷም መራመድ ስላቃታት ለገርንጊዳ አስታቀፈችው፡፡

ወደ ተባለችው አራስ ሲደርሱ አራሷ ለቅሶዋን ታስነካው ጀመር፡፡ ልጇ በጠና ታማ እንደሞተችባት ከነገረቻቸው በኋላ ነበር፡ ልጁን ተቀብላ ማጥባት የጀመረችው፡፡ ለገርንጊዳ የሚበላ ነገር ቢቀርብለትም ሊዋጠው አልቻም፡፡

# ፴፱

አክሎግ አዲስ ዘመን እንደደረሰ በቀጥታ ሮበርት ጋሎን ከማግኘቱ በፊት ቀንጠፋውን ለማነጋገር ፈለገ፡፡ ስልክ ደውሎ እንደጠራው ቀንጠፋውም ብቻውን ከነሮበርት ጋሎ ጋር የነበረበትንና ኢንጂነሩ ከጓዳ የታሠረበትን ቤት ለቆ ሜሮዳ ወደታሠረችበት ግቢ መጣ፡፡

"አንድ ነገር አስቤ ነው፡፡" አለ አክሎግ ለቀንጠፋው ሰላምታ ሳይሠጥ፡፡

"ምንድን ነው እሱ? መፍጠን አለብን፣ አጠር አርገህ ንገረኝ፡፡ ባለቀ ጊዜ የሚመጣ ሀሳብ እንደማይጥመኝ ታውቃለህ፡፡"

"ባለቀ ሰዓት የሚመጣ ሀሳብ አንዳንድ ጊዜ ጠቃሚ ነው፡፡ ልነግርህ የፈለኩት ስለሜሮዳ ጉዳይ ነው፡፡"

"ማለት....."ፈገግ አለ ቀንጠፋው፡፡ "ጥቂት ጊዜ ልስጥህ?..... ከእርሷ ጋር ልትተኛ ፈልገሃል? በርግጥ እኮ እኔ ብዙውን አዲስ አበባ ስለቆየሁ ላንተ ቅድሚያ መስጠት ነበረብኝ፡፡ ያው የፍላጎት ነገር ሆኖብኝ እንጂ አንተ በረሀ የቆየኸው ትብስ ነበር፡፡ አዲስ አበባ ሴት እንደልብ መሆኑን ታውቃለህ መቼም፡፡ ... እዚህ ስትባጅ ጊዜ ረስተኸው የጋለ ብረትህ ቀዝቅዟል?"

"እንደዛ አይደለም 'ንጂ ጊዜ ቢኖረኝ ደስ ይለኝ ነበር፡፡ ነገር ግን ጊዜ እንደቁምጣ አጥሮናል፡፡"

"እና ለምን ጊዜ ትገድላለህ አትናገርም?"

"ነገሩ እንዲህ ነው፡፡ ... የሜሮዳን መያዝ ሮበርት ጋሎ አያውቅም፡፡ አሁን ሳስበው ግን እርሷም ታስፈልገዋለች፡፡ ይህን የምልህ ልገድላት ጥቂት ደቂቃዎች በቀሩኝ ሰዓት ነው፡፡ መግደል ቀላል ነው፡፡ ሽጉጤም የተቀባበለ ነው፡፡ ነገር ግን ለሮበርት ጋሎ ይህቺ ሴት ታስፈልገዋለች፡፡ የቀድሞ የሲ.አይ.ኤ.

ወኪል የነበረች ሴት ናት፡፡ ኢንጂነሩን ከሎስ አላሞስ የምርምር ማዕከል በዴርቶጋዳ አባላት ያስጠለፈችው እሷ ናት፡፡ ... ይፈልጓታል፡፡ ጥቂት ክፍያ የሚጨምረን ከሆነ እርሷንም እንሸጥለት፡፡"

"ጐበዝ እኮ ነህ!" ቀንጠፋው ግንባሩን ግጥም አድርጎ ሳመው፡፡ "ይህን ነገር በፍጥነት አወያይቼው ልምጣ!"

"መልካም!" አክሎማ ሲጋራውን ለኮሰ፡፡ ከደቂቃዎች በኋላ ቀንጠፋው ተመልሶ ሮበርት ጋሎ በጉዳዩ ደስተኛ እንደሆነ ነገረው፡፡

"ክፍያውን ከፍ የማታደርጉት ከሆነ ችግር የለም ብሏል፡፡"

"እንዴት ነው ግን? እ? ... ቀለል አድርጐ አያት እንዴ?"

"የተሻለ ነገር እንደሚሰጠን አትጠራጠር፡፡ ያላንዳች ተጨማሪ ጥቅም በባዶ እጅ እርሷን ከመግደል ይሻላል፡፡ አለበለዚያም በኢንጂነሩ ሽያጭ ላይ ሜሮዳን እንመርቅለታለን፡፡ ለወደፊቱ ያለንን ግንኙነት ያጠናክረዋል፡፡"

"ደምበኛ ንጉሥ ነው፡፡" አክሎማ ፈገግ አለ፡፡

አክሎማና ቀንጠፋው ሜሮዳን ይዘው ኢንጂነሩ ታስሮ ወደሚገኝበት ቤት ይዘዋት ሄዱ፡፡

ከንድና ክንዱ ታስሮ ከዚሁ የወረደው የሰንሰለት ዘለበትም በፊት በኩል እንዲዞር ተደርጐ ሁለት እግሮችዋ ለየብቻ ታስረዋል፡፡ አንድ እጇ በመቆረጡ ለማሰር አልመች ብሎ እንጂ ከፍንጅና ፍንጇ ላይ ለማሰር ታስቦ የመጣ ሰንሰለት ነበር፡፡

ኢንጂነር ሻጊዝን ገብታ ስታይ አንዘፈዘፋት፡፡ አፏ በፕላስቲክ ባይታሸግ ኖሮ እንደምትለፈልፍ ሁሉም እርግጠኛ ነበሩ፡፡ ኢንጂነሩም እንደርሷው ታስሯል፡፡ አፉም ተለጉሟል፡፡

ሮበርት ጋሎ ከአክሎማና ከቀንጠፋው ጋር ወደ ታሠሩበት ክፍል መጣ፡፡

"ወደ ሀገራችሁ ልንወስዳችሁ ስለመጣን እንኳን ደስ ያላችሁ" አለ ሮበርት ጋሎ እንደ ፈንዲሻ ፈክቶ፡፡ ሻጊዝ ተወራጨ፡፡ ሜሮዳም ሰንሰለቱ እስኪበጠስ ወንበሩ ላይ

እንደቆሰለ አውሬ ሆነች፡፡ ሻጊዝ እስከ ወገቡ ወለሉ ላይ ተገለበጠ፡፡

"ሚስተር ሮበርት……" አለ አክሎግ ወደ ኢንጂነሩ አቆልቁሎ እየተመለከተ፡፡

"ኢንጂነሩን ወሊሶ ብናስጠምቀው መልካም ነበር፡፡ ለጠቅላይ ሚኒስትሩ ያዘዙላቸውን ጠበል እርሱም መጠመቅ ነበረበት፡፡ ጤነኛ አይመስለኝም፡፡ አታይም እንዴ ሚስተር ሮበርት! ይወራጫል እኮ!"

ሮበርት ጋሎ አክሎግ ያለው ባይገባውም ቀልድ መሆኑን በመተማመን ፈገግ አለ፡፡

"ብዙ ሳንዘገይ ብንንቀሳቀስ ሳይሻል አይቀርም" አለ ቀንጠፋው ወደ ሳሎን እንደተመለሰ፡፡ "እስከ ሞያሌ እንሸኛችኋለን፤ክፍያውን ግን አሁኑኑ እንፈልጋለን፡፡"

ሳምሶናይቱ ተከፍቶ የገንዘብ ቆጠራው ሲደረግ በርካታ ደቂቃዎች አለፉ፡፡ ከዚህ በኋላ ቀዩ ላንድ ክሩዘር ኢንጂነሩንና ሚሮዳን ወደ ሆዱ አስገባ፡፡ አክሎግና ቀንጠፋውም በግራና በቀኝ ገብተው ከመሀል አደረጓቸው፡፡ ሮበርት ጋሎም ጥቁሯን ሳጥን ይዞ ጋቢና ገባ፡፡ ሊላኛው የሮበርት ጋሎ ሰው የሆነ ነጭ ፈርጣማ ጐልማሳ ቀዩን ላንድ ክሩዘር በጥፍኑት ከግቢው አስወጥቶ ወደ ዋናዉ ጎዳና እንደገባ፣ ከአዲስ ዘመን ወደ አዲስ አበባ ፊቱን መልሶ ይፈተለክ ጀመር፡፡

5፡07

ለኮ/ል አሊጋዝ አስደንጋጩ የስልክ መልዕክት ደረሳቸው፡፡ አዲስ ዘመን ውስጥ የሻጊዝንና የሚሮዳን ጉዳይ እየተከታተለ የሚነግራቸው ሰው ነበር መልዕክቱን ያደረሳቸው፡፡ ሻጊዝንና ሚሮዳን ጭኖ ወደ አዲስ አበባ የሚፈተለከውን መኪና በራሱ

መኪና እየተከተለ ነበር የነገራቸው፡፡ ቀለሙን፣ ታርጋውን...የደረሰበትን...

...........................................

5፡11

...........................................

ዴር 33 በማቅርን ተራራ ላይ እሳት መትፋቷን አቁማ ወደ አዲስ ዘመን ተወነጨፈች፡፡

...........................................

"ብዙ ነዳጅ የለኝም ኮ/ል፡፡ የመኪናዬ ፍጥነት፣ ከሚኒቻቸው መኪና ፍጥነት ያነሰ መሆኑን ነግሬዎታለሁ፡፡"

...........................................

⁂

በአዲስ ዘመንና በወረታ መካከል ከሚገኘው የርብ ወንዝ አቅራቢያ ቀዩን ላንድ ክሩዘር የሚያሽከረክረው ነጭ ሰውዬ አንዲት ለየት ያለች አሞራ የመሰለች ድምፅ አልባ ነገር ከፊት ለፊቱ ባለው ሰማይ ላይ ዝቅ ብላ ስትበር አየ፡፡ ቆየት ብሎም የአንድ ረጅም ባህር ዛፍ ቅርንጫፍ ሲነካት ተመለከተ፡፡ ቅዠት ስለመሰለው ከቅርቡ ለተቀመጠው ሮበርት ጋሎ እንኳ ለመናገር አልደፈረም፡፡ ጥቂት ርቀቶችን ከፊት ለፊቱ በዝግታ ስትበር ከቆየች በኋላ አስቀደመችው፡፡

ለጥ ያለ ሜዳ ላይ ሲደርስ እንደገና ወደ ሰማይ ተመለከተ፡፡ ዝቅ ብላ በላዩ ላይ እየበረረች እንደሆነ ተገነዘበ፡፡ ወደሮበርት ጋሎ ሲመለከት እሱም ዓይኖቹን ጉልጉሎ ነበር፡፡

"ምንድን ነው?"

"አይተኸዋል?"

"አስደናቂ ነገር፡፡"

"እየተከተለን መሰለኝ፡፡"

"ዩፎ ይሆን?"

"የዩፎ ቅርጽ እንደዚህ አይደለማ!"

ይህን እየተነጋገሩ እያለ ዝቅ ብሎ የሚበረው የብረት አሞራ በድምፅ ማጉያ የሮበርት ጋሎን ስም ጥርት ባለ እንግሊዝኛ ጠርቶ፣ እንዲቆም ትእዛዝ ሰጠ፡፡

መኪናውን የሚያሽከረክረው ሰውዬ ግን ፍጥነቱን ለመጨመር ሞከረ፡፡ ጥቂት የመትረዬስ ጥይቶች ከፊት ለፊቱ ካረፉ በኋላ እንደገና "አቁም!" የሚለው ትዕዛዝ ከድምፅ ማጉያው ወጣ፡፡

ከዚህ ቀጥሎ ለመንዳት አልደፈረም፡፡ የመኪናውን ፍጥነት አቀዝቅዞ ወለል ባለው ሜዳ በሚያልፈው አስፋልት ላይ መኪናውን አቁሞ እጁን አንከርፍፎ ወረደ፡፡ ሮበርት ጋሎም ተከተለ፡፡

ወዲያው ከብረቱ አሞራ አራት አየር ወለዶች ዘመናዊውን "ሳት በሳት" መሣሪያ ታጥቀው ዱብዱብ አሉ፡፡ ሁሉቱም ጭንብል ለብሰዋል፡፡

ከቆመው መኪና ረበርት ጋሎ፣ አክሎግና ቀንጠፉው በፍጥነት ወርደው አየር ወለዶቱ ላይ ተኩስ ከፈቱባቸው፡፡ በፍጥነትም ሜዳውን ይዘው ተፈተለኩ፡፡ ሹፌሩም እየተኮሰ እነርሱን ተከተለ፡፡ራቅ ብለው ከተበታተኑ በኋላም ተኩሱን አፋፋሙት፡፡ አየር ወለዶቹ እየተከተሉ አቁስለው ለመያዝ ጥረት አደረጉ፡፡ ከአያሌ ደቂቃዎች የተኩስ ልውውጥ በኋላ ሹፌሩ ተመቶ ወደቀ፡፡ ቀጥሎ ሮበርት ጋሎ ጥይት ጨረሰ፡፡ አክሎግና ቀንጠፉውም ጋሎን ተከትለው ጥይት ጨርሰው ተያዙ፡፡ አራቱ ልዩ ስልጠና የተሰጣቸው አየር ወለዶች ሶስቱንም ፈጥርቀው ሲያበቁ አስፋልቱ ዳር ወደቆመው መኪና ይዘዋቸው ተመለሱ፡፡

የብረቱ አሞራ ወደፊት ጥቂት ከበረረ በኋላ ክንፉን ሰብስቦ ከሆዱ ባወጣቸው ጐማዎች አስፋልቱ ላይ አረፈ፡፡ ላፍታ ቆም ካለ በኋላ ፊቱን ወደ ነሱ መልሶ መጣ፡፡ ዳር ይዞ እንደቆመ ኮ/ል አሊጋዝ እና ጌራ መሣሪያዎቻቸውን ልጠው ወረዱ፡፡ ጌራ እንደነብር ተወርውሮ አክሎግን ለማነቅ ሊንደረደር ሲል ኮ/ል አሊጋዝ በምልክት ገሰፁት፡፡ ሶስቱንም ትጥቃቸውን ካስፈቱ በኋላ ነበር አንበርክከው የጠበቋቸው፡፡

"አክሎግ! አንተ ወስላታ አረመኔ! በሃያ አንደኛው ክፍለ ዘመን ሰው በሰንሰለት አሥረህ ያውም ወንድምህን ትሸጣለህ!?" ጌራ ጥርሶቹን አፋጬ፡፡ "ምን ያህል ለመኖር አስበህ ነው? ቀንጠፋው! ለስሙ የኢትዮጵያ ደህንነት ነህ፡፡ አለቆችህ ይህን ሰው ለመግደል ሞክረው ነበር፡፡ አልተሳካላቸውም፡፡ ለእነሱ እንኳ አልሆንክም፡፡ ክርስህ አምላክህ በመሆኑ እንደ ሰንጋ በሬ ለሽያጭ አቀረብከው! ለሁለታችሁ ምን አይነት ቅጣት ይበቃችሁ ይሆን? ሞትማ ለናንተ ታላቅ ስጦታ ይሆናል፡፡"

ጌራ አስፓልቱ ላይ ተንጎራደደ፡፡ "አክሎግ!" አለ መልሶ "እዚሁ ከፊታችን ያሰርከው ወንድምህን ፍታው! ከመኪናው አውርደውና ፍታው!"

አክሎግ ሻጊዝን ከመኪናው አውርዶ የሰንሰለቱን ቁልፍ ዳበሰ፡፡ ኪሱ ውስጥ አልነበረም፡፡ ረስቶት ነው እንጂ ሻጊዝን ሲሸጥ የሰንሰለቱን ቁልፍም ለሮበርት ጋሎ አስረክቦ ነበር፡፡

ሮበርት ጋሎ ቁልፉን ወረወረለት፡፡ የእግሩንም የእጁንም ቁልፎች ፈታለት፡፡ የአፉን ኘላስቲክም ላጠለት፡፡ ሻጊዝ ምንም ነገር መናግር አልፈለገም፤ ዕንባ ባይኑ ቀሮ ዝም አለ፡፡

ጌራ መሣሪያውን ለሻጊዝ ከሰጠ በኋላ ሻጊዝ ታስሮበት በነበረው ሰንሰለት አክሎግን ግጥም አድርጎ አሰረው፡፡ አፉንም ሻጊዝ ታስሮበት በነበረው ኘላስቲክ ለጐመው፡፡

ከዚህ በኋላ ቀንጠፋውንም በተራው ሜሮዳን እንዲፈታ አዘዘው፡፡ ሳያቅማማ እንዳዘዘው አደረገ፡፡

ሜሮዳ በታሰረችበት ሰንሰለት ቀንጠፋውን አስሮ ከቆለፈበት በኋላ አፉንም ሜሮዳ በታሸገችበት ኘላስቲክ አሸገው፡፡

ይህን ካደረገ በኋላ ወደ ሮበርት ጋሎ ዞረ፡፡

"እነዚህን ሰዎች በነፃ ትገዛኛለህ?" አለ ጌራ ታስረው ወደተጣሉት ሰዎች እያመለከተው፡፡ሮበርት ጋሎ ራሱን በፍርሃት ነቀነቀ፡፡

ጌራ ወደ መኪናው ገብቶ በግንዘብ የተሞላውን ሳምሶናይት ይዞ ወረደ:: ገንዘቡን ከአክሎግና ከቀንጠፋው ፊት ዘረገፈው:: የሁለቱም ዓይኖች ገንዘቡ ላይ ተተከሉ:: ይባስ ብሎ ወደ ዴር33 ገብቶ ያመጣውን ነዳጅ አርከፈከፈበት:: የሁለቱም ዓይኖች ፈጠጡ::

ጌራ ሁለቱንም አፈራርቆ ሲመለከት ከቆየ በኋላ ከአክሎግ ኪስ ክብሪት አውጥቶ ፈገግ አለ::

"ስንት ስንት ነበር የሚደርሳችሁ?!" ሲል ጠየቃቸው- አፋቸው መለጐሙን እያወቀ::

"አያችሁ!? መለጐም ምንምን እንደሚል ቀመሳችሁት!? የኢትዮጵያን ህዝብ እንዲህ ነበር ያደረጋችሁት:: ከዚህ በኋላ 'ነበር' ነው የሚቀራችሁ:: ነበር! ነበር!.... ውሃ ልናስገድብ ነበር! ባቡር ልንዘረጋ ነበር! ታክስ ልንቀንስ ነበር! ፍትህን ለማስፈን እየሞከርን ነበር! ሀገሪቷን በሙሉ ቀለበት መንገድ በቀለበት መንገድ ልናደርጋት ነበር! ሥልጣን በምርጫ ልንለቅ ነበር! ነበር!... ቂቂቂ... የኢትዮጵያ ገገርዎች ሁሌም ቢሆን 'ነበር'ን እንጂ 'ክብር'ን ይዘው ተሰናብተው አያውቁም:: ነበር! ነበር! ሃሃሃ.... የነበር አርበኞች! 'ለጉመን ነበር' ብለው ግን አያውቁም:: ካስለጓሚዎቹ ሁለቱ እናንተ ነበራችሁ! ይኸው 'ነበር' ብቻ ነው የቀራችሁ:: እሱንም ከዚህ በኋላ አታስታውሱትም::

"ከዚህ በኋላ ኢትዮጵያ ለለጓሚም ላስለጓሚም ትዕግስት አይኖራትም:: አንዱ ለጓሚ አልፎ ሌላኛው ለጓሚ ሲመጣ፣ አስለጓሚ እጁን ታጥቦ ከተፍ ይላል:: በዚያኛው የበላበትን አፉን ተጉመጥምጦ በምላሱ አፉን እየቀላጠፈ ሲመጣ ሲሄድ ኖሯል:: አክሎግ! ቀንጠፋው! ሃሃሃ... ከዚህ በኋላ ወዳዘጋጀሁት ገሃነም ወደሚባለው ሀገር እንጂ ይህቺን ገነት ሆና እያለች ሲኦል ያደረጋችኋትን ሀገር እንደገና አትለጉሚትም! ሴቶቿን ለአረብ፣ ምሁሮችዋን ለምዕራብ አትሸጡባትም!"

ጌራ ክብሪት ከኪ/ል አሊጋዝ ተቀብሎ ሲበቃ አንዲት ዕንጨት መዞ ጫረና ነዳጅ ወደ ተርከፈከፈበት ገንዘብ ወረወራት::

"ይህ አላግባብ ወደ ሀገራችን የገባ ህገወጥ ገንዘብ ነው! በዛ ላይ ደግሞ ሰው የተሸጠበት!" ጌራ ግው ብሎ የሚነደውን ገንዘብ እያየ ተናገረ፡፡"አላግባብ የመጣ አላግባብ ይቃጠላል!"

ሚሮዳ በፍጥነት ነዳጅ የያዘውን አነስተኛ ሰማያዊ ጀሪካን አንስታ ቆመች፡፡

አክሎማና ቀንጠፋው የሰንሰለታቸው ዘለበት እስኪሮጥ ተንፈራገጡ፡፡ ከእሳቱ ለማምለጥ ወደ ኋላ እየተንከባለሉ ሲሸሹ ነዳጁን በቀዬዎቱ ከእሳቱ ጀምራ እያፈሰሰች ተከተለቻቸው፡፡ እሳቱም ቀዬውን እቶናዊ ምላሱን መዞ የነዳጁን ጠብታ እየላሰ ተከተለ፡፡

ሚሮዳ ነዳጁን ለማርከፍከፍ እጇ እምቢ አላት፡፡

"እንዲህ ዓይነቱን እናንተ ናችሁ የተካናችሁበት፡፡" ብላ ቆመች፡፡ ወደ ሻጊዝና ይዞት ወደ ቆመው መግሪያ ዓይኗን ጣለች፡፡

ሻጊዝ ድንጋጤው ፊቱ ላይ በግልፅ ተነበበበት፡፡

"እና ወጥ አታማስልበት! ተኩሰዋ! አባቱ አርበኛ ነው ስትል አልነበር?!"

በዚሁ ቅፅበት ኮ/ል አሊጋዝ አክሎማና ቀንጠፋው ላይ የጥይት ቆሎ አፈሰሱና "እንዲህ ዓይነቱን አስቀያሚ ነገር ተላምጀዋለሁ"አሉ፡፡ "ጊዜ የለንም ጉበዝ!" ወደሮበርት ጋሎ አፈሙዛቸውን አዞሩ፡፡ "ምስጢሩን ለመጠበቅ ያህል!" አሉ ሁሉንም እያጠናቀቁ፡፡ "ለድፍረቱም ጭምር!"

ሶስቱም ጥቂት ከሳቁ በኋላ ሀጥ አሉ፡፡

# ፺

(ጅራፍ)

## ጣቅርን

ዴር33 ወደ ተራራው ከርስ ገብታለች፡፡ እነ ጌራ ለሽያጭ የተነዱትን ሰዎችና ጥቁሩን ሳጥን ይዘው ተመልሰዋል፡፡ ይህን የተነዱትን ሰዎችና ጥቁሩን ሳጥን ይዘው ተመልሰዋል፡፡ ይህን ብቻ አይደለም፤ እግረ መንገዳቸውን አዲስ ዘመን ከተማ ውስጥ ለህፃኑ ተበጥብጦ የሚሠጥ ወተት ይዘው ተመልሰዋል- ከተወለዱበት የመጀመሪያ ዕለት እስከ ስድስት ወራት ለህፃናት የሚሰጠውን ወተት፡፡

እነ ጌራ ወደተራራው ሲመለሱ ጦርነቱ አብቅቶ ነበር፡፡ እነ ሚራዥ ተራራውን የከበበውን ኃይል እንደጉም በትነው የተረፈውን ነድተው ከሸኙ በኋላ ተመልሰው ነበር፡፡

ዣንጊዳ ህፃኑን አጥቢ ፍለጋ ሲሄድ ያጀቡት ወታደሮች ወደ ተራራው ግርጌ ሲመለሱ ያልጠበቁት ነገር ነበር የገጠማቸው፡፡ ጦርነቱ ተጠናቆ እነሚራዥ ጠሩን ሸኝተው ሲመለሱ ነበር ተራራው ሥር የተገጣጠሙት፡፡

"ምን ይሻላል!?" ነበር ያሉት ዣንጊዳን፡፡

"ማንም አይነካችሁም! እናንተ በጐ ሰዎች! አለቃችሁ በህይወት ተርፎ ከሆነ አመስግኑልኝ፡፡ አውሬም ሆነ ሌላ መጥፎ ሁኔታ ካጋጠማችሁ ያስፈልጋችኋልና ትጥቃችሁን ማንም አያስፈታችሁም፡፡ ሂዱ! እናንተ በጐ ሰዎች! አመሰግናችኋለሁ! ጥንትም ቢሆን የኢትዮጵያ ወታደሮች ምስጉኖች እንጂ ምግባረ ብልሹዎች አይደሉም፡፡ ይህን ለጓደኞቻችሁ ንገሩልኝ፡፡ የኢትዮጵያ ሠራዊት የጥቂቶችን ራስ ጠባቂ ዘበኛ ሳይሆን፡ የህገሩ ጠበቃ መሆን እንዳለበት ንገሩት፡፡

"ለዚህ ህፃን ሲያድግ ይህን ታሪኩን እነግረዋለሁ፡፡ ...ሂዱ! ... የሚበላ የሚጠጣ እንዳላመጣላችሁ ይመሽባችኋል፡፡" ብሎ አሰናበታቸው፡፡ የሚላስ የሚቀመስ አለመኖሩን ስለሚያውቅ እንጂ እንዲህ መሸኘትስ አልፈለገም ነበር፡፡

ወታደሮቹ ራቅ ካሉ በኋላ "ለክርስትና እንመጣለን ገና!" በማለታቸው ሳቁን የለቀቀ አልታጣም፡፡

ዣንጊዳን ያስገረመው ሌላ ነገር ያጥቢዋ እመጫት ርህሩህነት ነበር፡፡

"እናቱ ምናልባት ድና ይሆናል፡፡ ከዚህ በኋላ እርሷ ታጠበዋለች፡፡" ብሎ ህፃኑን ይገፎ ልመለስ ሲላት "አይሆንም! መሞት መዳኗ ወዳልታወቀች እናት እንዴት ይህን መንጨረቅ ጨቅላ ትወስዳለህ?! ታልሆነ እኔም አብሬ ልሂድና ለጥቂት ቀናት አጥብቼው ልመለስ?" ነበር ያለችው፡፡ "በልጅ ይጨከናል እንዴ ባገራችሁ!?... ኧረ!... ይህማ አይሆንም!"

ወደዛው የወሰዷቸው አሮጊትም ህፃኑ ያለ አጥቢ መሄድ የለበትም ብለው በመቃወማቸው አሮጊቷን ቤታቸው አስገብተው በእመጫቷ ልጁን አሳቅፈው ነበር ወደ ተራራው ሥር የተመለሱት፡፡ በዚህ ጊዜ ግን እነ ጌራ ተመልሰው ነበር፡፡ ለልጁ ተበጥብጦ የሚሰጠውን ወተትም ይዘው በመምጣታቸው ጡት አስፈላጊ መሆኑን ቢያምኑም የሲጳራን መዳን በመተማመን እመጫቷን ሴትዮ አመስግነው ወደ ቤቷ መልሰው ነበር ወደ ተራራው የገቡት፡፡ ሁሉም ወደ ተራራው ከገቡ በኋላ የሞተ ሲቀብሩ የቆሰለ ሲያክሙ ሌሊቱን አጋመሱት፡፡ ኪራኮስም፣ ሲጳራም ከሰመመናቸው እስከአሁን አልነቁም፡፡

ጌራ ኪራኮስ የነገረውን ምስጢር ሁሉ ለሚራኘ ነግሮታል፡፡ በመሆኑም አሁንም ቢሆን አጣብቂኝ ውስጥ መሆናቸው ገብቷቸዋል፡፡ የሸኙት ጦር ኃይሉን በማጠናከር ተመልሶ ሊከባቸው እንደሚችል አምነዋል፡፡ ተራራውም በጦር ጀቶች ላለመደብደቡ እርግጠኛ አይደሉም፡፡ ከዚህ የተነሣ የምድር ውስጡን መንገድ የመክፈቱና የመሰወሩ ጉዳይ ጊዜ የሚሰጠው እንዳልሆነ ተገንዝበዋል፡፡አስቸጋሪ ሆኖ የተገኘው የኪራኮስ ከሰመመኑ አለመንቃት ነው፡፡

ሚራኘ በአግራሞት የኪራኮስን አባት ማስታወሻ ከጌራ ተቀብሎ ሲያነብ ቆዬ፡፡ በጥርጣሬ ያያቸው የነበሩት የነአክሎግ ማንነት ቀድሞ የታወቀ መሆኑን ሲያውቅ ደነገጠ፡፡

"ታዲያ ኪራኮስ ከሰመመኑ እስኪነቃ ከምንጠብቅ ለምን እኛ አንሞክረውም? ... ቁልፉ እንደሆነ በእጃችን ነው፡፡ ኪራኮስም ማስታወሻውን የተረዳው በማንበብ ብቻ ከሆነ... ማለቴ በቃል ማስታወሻውን የተረዳው በማንበብ ብቻ ከሆነ... ማለቴ በቃል የነገሩት ከሌለ እኛም በገባን መሠረት ዋሻውን መክፈት እንችላለን፡፡ አይደለም እንዴ?" ሲል በዙሪያው የተኮለኮሉትን ጠየቀ-ሚራዥ፡፡ ዣንጊዳ፣ ሻጊዝ፣ ሚሮዳ፣ ጌራ እና ሳዶፍ የማስታወሻው ምስጢር አስደምሟቸው ከበው እያዩት ነበር፡፡

"ለግሉ በቃል የነገሩት ነገር አይኖርም ብለህ ነው?" ሲል ሻጊዝ ጠየቀው፡፡

"እስኪያቅተን መሞከሩ አይከፋም፡፡'ከሞከርነው ነገር ይልቅ ያልሞከርነው ነው ሚቆጨኝ' ብሏል ታላቁ ገጣሚ...." ጌራ ማስታወሻውን ተቀብሎ ይበረብረው ጀመር፡፡

ቁልፉ ከወጣበት የማስታወሻው ገበታ ውስጥ ጣቶቹን ስደ ሲያተረማምስ፣ አንድ የተጣጠፈ ወረቀት ይዞ ወጣ፡፡ በተራራው ከርሰ ምድር ያለው ዋሻ ካርታ ነበር፡፡ እነ ጌራ አሁን የቆሙበትን ክፍል ጨምሮ ሁሉም ክፍሎች ካርታው ላይ ተቀምጠዋል፡፡

በካርታው ላይ ከተቀመጡት ክፍሎች ውስጥ ጥንታዊውን ስልጣኔ መመርመሪያ ከሆነውና ዣንቶዣራ በተባለው ክፍል ላይ የቁልፉ ምልክት ተቀምጦ ተመለከቱ፡፡ ሁላቸውም ተንጋግተው ወደ ዣንቶዣራ ገቡ፡፡

ጣራና ግድግዳውን ከዚህ ከዚህ ቀደም አይተውት አያውቁ ይመስል በዓይኖቻቸው ይዳስሱት ገቡ፡፡ ከሌሎች ክፍሎች በተለየ መልኩ ይህ ክፍል በጥቅሶች፣ በምልክቶችና በስዕሎች የተሞላ ነው፡፡ከዚህ ቀደም በተደጋጋሚ ላልገባ ሰው የፍርሃት መንፈስ የሚለቅ አስፈሪ ክፍል፡፡

በስተምዕራብ በኩል ካለው ግድግዳ ላይ ግዙፍ የዘንዶ ስዕል ይታያል፡፡ ምላሱን እንደ ሰይፍ የመዘዘ ዘንዶ፡፡ ምላሱ ለጥቂት ሊነካት ያለች ቁልፍ ደብዘዝ ብላ ተስላለች፡፡

ሚራዥ በኪራኮስ አባት ማስታወሻ ገበታ ውስጥ የተገኘችውን ቁልፍና ግድግዳው ላይ የተሳለችውን ቁልፍ አስተያያቸው፡፡ ልዩነት የላቸውም፡፡

ሁሉም ወደ ቁልፏ ቀርበው ተመለከቱ፡፡ በዘንዶው ምላስና በቁልፏ መካከል ባለች አነስተኛ ቦታ ላይ ትንሽዬ ቀዳዳ አዩ፡፡

ሚራዥ በዝግታ የቁልፉን ጫፍ ወደ ትንሽዋ ቀዳዳ ሰዶ ወደ ግራም ወደ ቀኝም አጠማዘዘ፡፡ አልተከፈተችም፡፡ ስቦ ሊያወጣት ሲሞክር ልትወጣለት አልቻለችም፡፡ እዛው ውስጥ እንዳለች መጀመሪያ ወደ ግራ ብዙ ጊዜ አሽከረከራት፤ የተከፈተ ነገር የለም፡፡ ቀጥሎ ወደ ቀኝ እንዲሁ አደርጎ ቁልፉን ለማውጣት ሳበ፡፡

በዚህ ጊዜ የፖስታ ቤት ሳጥን በር የምታክል በር ተከፈተች፡፡ በውስጧ ከቁራጭ ወረቀት በቀር ምንም አላገኙም፡፡ ጀሮ የምታክል የብራና ወረቀት፡፡

ቁራጯን ብራና አነበባት፡፡
"ጀርባህን ተመልከት" ትላለች፡፡

ሁሉም ወደ ጀርባቸው በአንድነት ዞሩ፡፡ ከማዶ ካለው ግድግዳ ላይ ምንም ነገር አላዩም፡፡ የተቀመጡት ከዚህ ቀደም የሚያውቋቸው ጥቅሶች ብቻ ናቸው፡፡
"ግልቡን ሥልጣኔ መግለብ"
"የጥንቱን አሁን መመርመር"
"ራስን መመልከት"...የሚሉና ሌሎች ሀረጎች ናቸው የሰፈሩት፡፡
"ጀርባህን ተመልከት"
"ጀርባህን ተመልከት"
"ጀርባህን...." ደጋገሙት፡፡ ጠብ የሚል ሀሳብ አልተገኘም፡፡

ሻጊዝ ቁራጯን ብራና እያገላበጠ ሲያያት ቆይቶ ቀና አለ፡፡ ሁሉም አፋፉን አዩት፡፡
"ይህ መልእክት የተፃፈው አንድ ቁልፉ በእጁ ይገባል ተብሎ ለታመነበት ሰው መሆን አለበት፡፡ ጀርባህን ተመልከት

የሚለው መልእክት ተራ ትምህርት ብቻ አይመስለኝም፡፡ ስለዚህ በሽማግሌው ማስታወሻ ላይ እንደተረዳነው ማህደሩ የተፃፈው ለኪራኮስ ነው፡፡ በኪራኮስ ጀርባ ላይ የተተወ ነገር ሳይኖር አይቀርም፡፡" ሻጊዝ ይህን ከማለቱ ሁሉም ኪራኮስ ወደሚታከምበት ክፍል ሂደው ገቡ፡፡

ኪራኮስ እስከ አሁን ከስመመኑ አልነቃም፡፡ዶክተሩን አስፈቅደው ጀርባውን ተመለከቱት፡፡

በኪራኮስ ጀርባ ላይ አራት መስመር ግጥም ተገኘ፡፡ በደበዘዘ ንቅሳት የደበዘዙ ስንኞች፡፡የስንኞቹ አፃፃፍ የቁም ፅሁፍ ሆኖ በሽማግሌው ማስታወሻ ላይ ካለው የብዕር አጣጣል ጋር ተመሳሳይ ነው፡፡ ግጥሙን ሁሉም ተሻምተው አነበቡት፡፡

*በተሰጠህ መክሊት በተሰጠህ መፍቻ*
*ደጋግመህ ካልከፈትክ ስጥህ መባቻ*
*የዘንዶው ጭንቅላት ካልተቀጠቀጠ*
*ሲወፍር ይኖራል ሰንተን እየዋጠ*

ይላሉ ስንኞቹ፡፡ ስርአተ ነጠጥብ የላቸውም፡፡ስንኞቹን ፅፈው ከያዙ በኋላ በየግላቸው ያሰላስሏቸው ጀመር፡፡ አሁንም ወደ ሻጊዝ ሁሉም ተመለከቱ፡፡

"ደጋግሞ መክፈትና የዘንዶውን ራስ መቀጥቀጥ የሚሉ መልእክቶች ይመስለኛል በነዚህ ስንኞች ውስጥ የተቀመጡት፡፡" ሲል ገለፀ ሻጊዝ፡፡ "ቁልፋም ይሄው ነው፤ የመጀመሪያው፡፡"

ሁሉም ሲያዩት ከቆዩ በኋላ ዣንቶዣራ ወደሚባለው ክፍል ተመለሱ፡፡

ሚራኘ የፖስታ ቤት ሳጥን የምታክለዋን ሽንቁር የእጅ ባትሪ አብርቶ መረመራት፡፡ በስተግራ በኩል የመጀመሪያዋን የምትመስል የቁልፍ ማስገቢያ ቀዳዳ ተመለከተ፡፡

ቁልፏን ሰዶ አሁንም ወደ ቀኝ አሽከርክሮ ሳባት አልተከፈተችም፡፡ እንደገና ወደ ግራ አሽከርክሮ ሲስባት ተከፈተች፡፡

ከዚህች ሽንቁር ውስጥም በቁራጭ የብራና ወረቀት ላይ የተፃፈች ፅሁፍ ነበር ያገኙት፡፡

ሚራዥ ጽምፁን ዘለግ አድርጎ አነበባት፡፡ ሁሉም በየተራ ቢያነብ ጊዜ ላለመፍጀት በማሰቡ ይሆናል፡፡ እንደገመተው ከሌላ አካባቢ ተጉዞ የመጣ ጦር ሊከባቸው ይችላል፤ አልያም በከባድ መሣሪያም ሆነ በጀት ተራራው ተደብድቦ ሊያልቁ ይችላሉ፡፡ ድምጹን ዘለግ አድርጎ የጥድፊያ ንባቡን አንበለበለ፡፡

“ንግግሬን የማታስተውሉ ስለ ምንድን ነው? ቃሌን ልትሰሙ ስለማትችሉ ነው፡፡ እናንተ ከአባታችሁ ከዲያብሎስ ናችሁ፡፡ የአባታችሁንም ምኞት ልታደርጉ ትወዳላችሁ፡፡ እርሱም ከመጀመሪያ ነፍስ ገዳይ ነበረ፤ እውነትም በእርሱ ስለሌለ በእውነት አልቆመም፡፡ ሐሰትን ሲናገር ከራሱ ይናገራል፡፡ ሐሰተኛ የሐሰትም አባት ነውና፡፡ እኔ ግን እውነትን የምናገር ስለሆንሁ አታምኑኝም፡፡ ከእናንተ ስለ ኃጢአት የሚወቅሰኝ ማን ነው? እውነት የምናገር ከሆንሁ እናንተ ስለምን አታምኑኝም?” ይላል ጥቅሱ፡፡

“ምንድን ነው!”

“ሽማግሌው ተፀፅተው መናዘዛቸው ይሆን?!”

ሁሉም በየፊናው የራሱን ግምት አስቀመጠ፡፡

ሚራዥ ይህ ጥቅስ ከዮሐንስ ወንጌል ከመወሰዱ በቀር ሌላ ፍንጭ ሊሰጠው አልቻለም፡፡እንደገመተው “እመነኝ፣ደጋግመህ ክፈት፡፡” ለሚል መልእክት እና እግረ-መንገዱንም ለማስተማር የተቀመጠ ጥቅስ ከመሆን ያለፈ ፋይዳ የለውም ሲል ደመደመ፡፡

በእጁ ባትሪው ሌላ ሽንቁር ሲፈልግ ቆይቶ አገኘ ከፈተው፡፡ ከዚህም ውስጥ ከጥቅስ በቀር ሌላ ያገኘው ነገር አልነበረም፡፡

“ወንድሞች ሆይ፣ እናንተ የተማራችሁትን ትምህርት የሚቃወሙትን መለያየትንና ማሰናከያን የሚያደርጉትን ሰዎች እንድትመለከቱ እለምናችኋለሁ፡፡ ከእነርሱ ዘንድ ፈቀቅ በሉ፡፡ እንደዚህ ያሉት ለገዛ ሆዳቸው እንጂ … ለሕሊናቸው አይገዙምና፡፡ በመልካምና በሚያቆላምጥ ንግግርም ተንኮል የሌላቸውን ሰዎች ልብ ያታልላሉ፡፡ …ስለ በጎ ነገር ጥበበኞች ለክፉም የዋሆች እንድትሆኑ፡፡ የሰላምም አምላክ ዘንደውን ከእግራችሁ በታች ይቀጠቅጠዋል፡፡”

“ይህስ ቢሆን ምንድን ነው?!”

“ሽማግሌው አውቀው እያጃጃሉን ነው!”

"ምስጢሩን አርቀው ለመቅበር እንጂ ሊሰብኩን መቼም አይሆንም!"
በዚሁ ብራና ጀርባም በዘፍጥረት መፅሐፍ ላይ ተጽፎ የሚገኝ ጥቅስ ሰፍሯል፡፡ "እርሱ ራስህን ይቀጠቅጣሀል፡፡" የሚለው ጥቅስ፡፡

ሚራዥ ጥቅሱን አንብቦ ሲያበቃ ለሮሜ ሰዎች የተፃፈ መልእክት መሆኑን ከተረዳ በኋላ "ህሊና" የሚሉና "ዘንዶ" የሚሉት ቃላት ግን በምትክ የገቡ መሆናቸውን ተናገረ፡፡ "ይህ ዘንዶ የሚለው ቃል ስለተደጋገመ ምናልባት ጉዳዩ ያለው ከዘንዶው ዘንድ ሳይሆን አይቀርም" ሲል አከለ፡፡ ሆኖም ቀጣዩን ሽንቁር ፈልጎ ከመክፈት ወደ ኋላ አላለም፡፡

"ጉበዝ ስንከፍት እንዳንከርም እንግዲህ፡፡ ተራራው በሚግ ሊደበደብ ይችላል እኮ፡፡" አለ ሳዶፍ፡፡ "ዝም ብለን ለምን በግድግዳው ላይ የተሳለውን ዘንዶ በመዶሻ አንቀጠቅጠውም!?"

ሚራዥ በዚሁ ቅፅበት ሌላ ብጣቂ ጥቅስ አወጣ፡፡
"ልክ ነው!"ሲል ጮኸ ተናገረ፡፡ "ቁልፉ ዘንዶውን መቀጥቀጥ ነው፡፡"

ሚራዥ ያገኛት ብጣቂ "በዚህ በኩል መንገድ የለም፡፡ መንገዱ የዘንዶውን ራስ በመቀጥቀጥ ይገኛል፡፡" የምትል ናት፡፡ በዚሁ አፍታ ሳዶፍ እየሮጠ ሄዶ መዶሻ ይዞ ተመለሰ፡፡
"ቀስ ብለህ ሳዶፍ! የዘንዶውን ራስ ስትቀጠቅጥ ሌላ ነገር አብሮ
እንዳይናድ፡፡" ሻጊዝ የመዶሻው ራስ የዘንዶውን ራስ ሲቀጠቅጥ እየተመለከተ፡፡

"ቅኔያዊ ነው ንግግርህ" አለ ሚራዥ ወደ ሻጊዝ ዞር ብሎ፡፡ "እኛ ኢትዮጵያውያን መገንባትና መናድ እጣ ፈንታችን ቢሆንም፣ ሁለቱንም በጥበብ ለማድረግ አልታደልንም፡፡የሠራነውን ስንንድ ናዳው ራሳችን ላይ እየወረደ መቃብራችን ሲሆን ኖሯል፡፡ መሠረቱን አላገኘነውም፡፡ የዛሬን መኖርንም ሆነ ነገን ማበጀት አልቻልንም፡፡"

ሣንጊዳ የሳዶፍን መዶሻ ተቀብሎ የዘንዶውን ራስ ይናገር ጀመር፡፡ መዶሻውና ቃላቱ እኩል የዘንዶው ራስ እየቀጠቀጠ ያርፉ ይመስሉ ነበር፡፡

"ይኸውና መንገዱ እየተከፈተ ነው፡፡ ሚራዥ... ባለፈው 'ትውልዱን ማዘጋጀት' ስትል የተናገርከው ነገር እስካሁን ከአእምሮዬ አልጠፋም፡፡ የግልቡ ስልጣኔ ወበቅ የትናንቱንም የዛሬውንም የነገውንም እንዳይደብቅ ከኢምንት ውስጥ ማንነታችን ለመፈልቀቅ የሣንቶሣራን መንገድ በመጠባበቅ ላይ ነን፡፡ ግልቡን ስልጣኔ እስክንገልብ ረሀብም ጦርነትም ስደትም እንድናፈገፍግ አያደርገንም፡፡"

ከብዙ ቅጥቀጣ በኋላ የዘንዶው ራስ ወደ ውስጥ እየገባ ሂደ፡፡ ቆይቶም በኮንክሪት የተሠራው የውስጥ ለውስጡ መንገድ በር ተበረገደ፡፡ ጩኸትና እልልታ ቀለጠ፡፡ በረሃብ የተዳከመው ሁሉ በተስፋው ጭላንጭል ተበረታታ፡፡

# ፴፩

(ኪርያላይሶን)

"ፈጠን ፈጠን በሉ ጎበዝ፣ ተራራው ሊደበደብ ይችላል። ዕቃ ሸክፉ፤ አንድም ነገር እንዳንረሳ ይሁን። እንኳን ዕቃችን ጥላችንም እዚህ መገኘት የለበትም...." እያለ በየክፍሉ እየገባ ነበር ጓዛቸውን ሁሉ አስቀድሞ የተወከለው ሰው ሲያሸክፍ የቆየው። የምድር ውስጡ መንገድ በር ከመከፈቱ አስቀድሞ እቃው ሁሉ ተቀርቅቦ ተዘጋጅቶ ነበር።

ሚራኘ በሩ ከመከፈቱ እየበረረ የሄደው ወደ ህክምና ክፍሉ ነበር። በሕይወት የተረፉት ሦስት ቁስለኞች ብቻ ነበሩ። ሌሎች በክብር የተቀበሩት ቀደም ብሎ መሆኑ ተነገረው። ያልለየላቸው ሦስቱም ቢሆኑ በጥሩ ጤንነት ላይ አልነበሩም። ኪራኮስና ሲጻራ ዓይኖቻቸው አልተገለጡም። ሲጻራ ልጇን አቅፋ አልሳመችም፤ ኪራኮስም የበሩን መከፈት አላየም።

እነዚህን በጠና የቆሰሉ ሰዎች በምድር ውስጡ መንገድ ይዞ መጓዝ እንደማይቻል ታምኖበታል። በመሆኑም ህክምና ሰጪ ሰዎችና ቁስለኞቹን ጭኖና ዴር33 ከተራራው በመመንጠቅ ወደ ጣና ሐይቅ ከበረረች ቆይታለች።ዴር33 ሌሎቹን ስለማትይዝ ከህክምና ቡድኑና ከቁስለኞቹ በተጨማሪ ሚሮዳ ህጻኑን ለመንከባከብ ገብታለች። ጌራም የዴር33ን መሪ ጨብጧል።

በሌላ በኩል አንዳንዱ ያቅሙን አንዳንዱ ካቅሙ በላይ ተሸክሞ ቀሪውም እቃ በእጅ ጋሪዎች እየገፉ የምድር ውስጡ ጉዞ ተጀምሯል።

"ባትሪዎቻችን እንዳያልቁ ተጠንቀቁ። በረሃብ የደከመ ካለ ያልደከመ ሸክሙን ያግዝ! አይዞን! አይዞን! እንበርታ! እንደገና ዳጋን ልናዩው እየሄድን ነው!" አለ አንድ ሰው ከመሃል።

"አባቶቻችን ታላቅ ነበሩ!" አለ ሌላው ከመሃል።

"ኢትዮጵያ ታላቅ ነበረች!" ብዙ ድምጾች ተሰሙ…
"ግልቡ ሥልጣኔ ይገለባል!"
"ጉዞ ወደ ታላቅነት"
"ጉዞ ራስን ወደ ማግኘት!"

ጊራኘ፣ ገርንጊዳ፣ ሳዶፍና ሻጊዝ ከኋላ ቀርተው ዋሻውን መልሰው ዘርግተው ነበር መከተል የጀመሩት:: የኮንክሪቱን በር ለመክፈት የዘነጉዱውን ፍንቅላት ሲቀጠቅጡ ወደ ውስጥ ተሰርጉዶ የገባው ራስ የምድር ውስጡን በር ከዋሻው ኮንክሪት ጋር ሰፍቶ የያዘ ወፍራም ብረት ነበር:: ከውስጥ በኩል ይህንኑ ብረት ወደ ነበረበት ቀዳዳ ከትተው ከውስጥ ለመደብደብ ሌላ ጥበብ አላስፈለጋቸውም:: ይህን ከማድረጋቸው በፊትም የፖስታ ሳጥን የምታክለውንና ምስጢሩ የተቀመጠባትን ሽንቁር በራሷ ቁልፍ ዘግተዋት ነበር የገቡት::

ከፊት የቀደማቸው ተጓዥ ርቋቸዋል:: የየድርሻቸው ሸክምም ተቀምጦላቸው ነበር:: ሸክማቸውን ተሸክመው ወደፊት ገሰገሱ::

ወደ ተጓዡ እየቀረቡ ሲመጡ የመዝሙር ድምጽ እየቀረባቸው መጣ:: የተለመደው የዴርቶጋዳ መዝሙር::

"ዴርቶጋዳ ዴርቶጋዳ ዴርቶጋዳ
ዴርቶጋዳ ዴርቶጋዳ ዴርቶጋዳ
ማንም ሰው ላይመጣ እኛን ለመለወጥ
እናፈገፍግም እናቅማማም ለለውጥ::
ያቀረቀርክበት አንገት ያስደፋህ ቀን
ነግቷል ብለህ ተነስ ፍዳና ስቀቅን::
ለውጥ ለማምጣት አናቅማማም
አናፈገፍግም ለፍቅር ሰላም
ትውልድ ለማንጻት ከህሊና ዕዳ
ቃላችን ቃል ነው ዴርቶጋዳ::
ዴርቶጋዳ ዴርቶጋዳ ዴርቶጋዳ
ዴርቶጋዳ ዴርቶጋዳ ዴርቶጋዳ
በባዕዳን ምድር የሰው ጎጆ ሳጋ
በእናት ሀገር ጓዳ ሰባተኛ ዜጋ
እስከመቼ ድረስ እንቅብ በዕንቅብ ላይ
አሜን እንላለን ሲደፋብን ከላይ?

ለውጥ ለማምጣት አናቅማማም
እናፈገፍግም ለፍቅር ሰላም
ትውልድ ለማንጻት ከሀሊና ዕዳ
ቃላችን ቃል ነው ዴርቶጋዳ
ዴርቶጋዳ ዴርቶጋዳ ዴርቶጋዳ
ዴርቶጋዳ ዴርቶጋዳ ዴርቶጋዳ
ተስፋ ያስቆረጡን እስኪቆርጡ ተስፋ
ሰው መሆናችንን እስኪያምኑ በይፋ
ምን ቢረቅ ምን ቢጠልቅ የቅጥረኛ ሴራ
አናፈገፍግም እስከ ዣንቶዣራ..."

"ረሃባቸውን ለማስታገስ ይሆናል የሚዘምሩት" አለ ሳዶፍ እየቀረቡ ሲመጡ፡፡

"ለዛ ብቻ እንኳ አይመስለኝም... የተሰበረ ቅስማቸው እንደገና ስለተመለሰ ሳይሆን አይቀርም" ሻጊዝ ርምጃውን አፋጠነ፡፡ "ሚራዥ ከፊት እንቅደም፡፡ መብራት እንዳያልቅ፡፡"

"እኔና ሳዶፍ ሰው ደክሞ እንዳይቀር ከኋላ እንከተላለን፡፡" አለ ዣንጊዳ፡፡

ሚራዥና ሻጊዝ "እይዞን!" እያሉ ወደ ፊት ቀደሙ፡፡

የምድር ውስጡን መንገድ ለሰዓታት ተጓዙ፡፡ ሊሊቱ ይንጋ አይንጋ ሊገነዘቡ አልቻሉም፤ የሁላቸውም ሰዓት መስራት አቁሞ ነበር፡፡

"ይህ ጉዳይ መጠናት አለበት፡፡" አለ ሻጊዝ በሁኔታው በመገረም፡፡ "ከጊዜ ውጭ መሆን ይቻላል ማለት ነው ወይስ ሰዓቶቻችን የተሠሩባቸው ቁሶች ከዚህ ሁኔታ ጋር ባለመዛመዳቸው ነው?"

መንገዱን እየገፉ ሲመጡ የእጅ ባትሪዎች ሁሉ መጥፋት ጀመሩ፡፡ ባትሪዎቻቸው በማለቁ አለመሆኑን የተረዱት፣ አዳዲስ ባትሪዎችን አጉርሰውም አልሰራ በማለታቸው ነው፡፡

ሆኖም ጉዟቸውን አልገቱም፡፡ አንዱ ያንዱን ጀርባ ይዞ በጨለማው ውስጥ ይጓዝ ጀመር፡፡ ከፊት ያለው ሚራዥ በመሆኑ በዳበሳ እንዲመራ ሽክሙን ሌሎች ተከፋፍለው ይዘውታል፡፡

"መለኮሻ የያዘ ይኖራል?" ሲል ሚራዥ ጠየቀ እንደዚህ ለረጅም ጊዜ ከተጓዙ በኋላ፡፡ "መለኮሻ! መለኮሻ!"

ከወጥ ቤቱ ኪስ መለኮሻው ተገኘ፡፡ ይህ 'ላይተር' መሰል አነስተኛ መለኮሻ ውስጡ ዱቄት መሰል ውህድ ሲኖረው ጎኑ ላይ ጫን ሲደረግ እሳት እንዲተፉ ሆኖ እዛው በድርጅቱ የተሠራ ነው፡፡እሳቱም ሆነ ውስጡ ያለው ቅመም አያልቅም፡፡

ሚራዥ የለበሰውን ኮት አውልቆ በአንዱ የብረት ዘንግ ላይ በሽቦ አሠረው፡፡ ምን ሊያደርግ ነው ብለው ሲጠባበቁ የነበሩት ሁሉ ኮቱን ለኩሶ የብረት ዘንጉን ከፍ ሲያደርገው ነበር ዋሻውን በሳቅ ያናጉት፡፡

"የኛም ኮት ይበራል! እኛም ኮታችን እንሰጣለን! ሲያልቅብህ ንገረን!"

"ጉበዝ ኮት ወደፊት አስተላልፋ!"
"ጃኬትም! ሸሚዝም! እንቀበላለን!"

ሚራዥ በኮቱ መብራት ወጋጋን ሲመራ ከቆየ በኋላ ሸሚዙንም ለኮሰ፡፡ እሱም ሲያልቅ ሱሪውን አወለቀ፡፡ ተገልግሎ እሺ አላለም፡፡ በቁምጣው ሆኖ ሱሪውን ለኩሶ እያበራ መንገዱን ቀጠለ፡፡

"ዘምሩ! ዘምሩ!" አለ ሚራዥ ላፍታ ቆም ብሎ፡፡ "እንደርሳለን! ዘምሩ!"

የዋሻው ውስጥ መንገድ ንብ እንደሚተምበት የአበባ ወቅት ሜዳ "ህም ህም!" ይል ጀመር፡፡

በመቀጠል ሻጊዝ ኮቱን ለመብራት ለኩሶ በሚራዥ ፊንታ ህዝቡን መምራት ጀመረ... ኮቱ ሲያልቅም ሸሚዙን፡፡ ይህም ሲያልቅ ሱሪውን፡፡

"እንደርሳለን! ገና ብዙ ኮት፣ ሸሚዝና ሱሪ አለን፡፡ ክራባት ያለውም ያምጣ፡፡ ከቆዳችን በቀር የማናበራው አይኖርም!" አለ ሻጊዝ ያለውን ሲጨርስ፡፡ "መዝሙሩን! መዝሙሩን! መዝሙሩን ቀጥሉ!"

በዚህ ሁኔታ ከሰዓታት ወዲያ ከኋላ ካሉት ጥቂት ሰዎች በቀር ከፊት ያሉት ዕርቃናቸውን ቀርተው ነበር፡፡ የእርቃኑ ጉዞ ቀጠለ፡፡

ከአያሌ ጉዞ በኋላ፣ ሚራዥ እንደገና እየመራ ቆይቶ ብዙ ርቀት ሄደው በድንጋጤ ክው ብሎ ቆመ፡፡ ያየውን ማመን አልቻለም፡፡ የዋሻውን ውስጥ መንገድ የቆመ ውሃ ተነጥፎበት ነበር የመለከተው፡፡

ሁኔታውን ከኋላው ለሚጓዙት በሀዘን ገለፀ፡፡ ደፍሮ ወደ ውሃው ይዟቸው እንዳይገባ ጥልቀቱን አያውቅም፡፡ ጣና ውስጥ መሆናቸውን ግን ውሀው አመለከተው፡፡
ሚራዥ ሌሎቹ ባሉበት እንዲቆሙ ካዘዘ በኋላ ወደ ውሃው ለሙከራ ገባ፡፡

ቀስ በቀስ እግሮቹ እየጠለቁ መጡ፡፡ እየገፋ ሲሄድ ውሃው እስከ ወገቡ ደረሰ፡፡

"እንደገና መመለሳችን ነው በቃ?!"
"ወደ ኋላማ አንመለስም!"
"እና እንደ ፈርዖን ሠራዊት እዚሁ ሰጥመን እንቅር?!"
"እንደገና ልንፋለም?"
"እንፋለማለና!ሌላ ምን አማራጭ አለን?!" ሁሉ በየፊናው ይብላላ ጀመር፡፡

ሚራዥ በዋና ጉዞውን ጀመረ፡፡ አስር ሜትር ያህል ከዋኘ በኋላ ከፊት ለፊቱ ድምፅ የሰማ መሰለው፡፡

ፍጥነቱን በጨመረ ቁጥር ከፊት ለፊቱ የተሰማው ድምፅም እየጠራ መጣ፡፡

"ደርሰዋል! ደርሰዋል! የሙብራት ወጋገን እየታየኝ ነው!" ድምፁ የጌራ ድምፅ መሰለው::

"በውሃው ተደናግጠው ወደኋላ እንዳይመለሱ..." ይህኛው የሜሮዳ ድምፅ መሆኑን አልተጠራጠረም:: "ፍጠን! ፍጠን! በድም ማጉያው መድረሳቸውን ንገራቸው!"

ሚራዥ ሲዋኝ የሚያንቦጫርቀውን ውሃ ድምፅ ለመቀነስና በውል ለማዳመጥ ሲል መዋኘቱን ገታ::

"ወደ ኋላ እንዳትመለሱ! ደርሳችኋል!.... ወደ ኋላ እንዳትመለሱ!" የድምፅ ማጉያው በዋሻው ውስጥ አስተጋባ:: "የመጀመሪያው ዴርቶጋዳ ሲፈነዳ የገባ ውኃ ነው!"

ይህን ተከትሎ ከሚራዥ ኋላ ጉዞውን የገታው ተጓዥ ዋሻውን የሚያንቀጠቅጥ ድምፅ አሰማ:: የድል ድምፅ... እልልታና ሆታ....

"ጀልባዎች አሉን! ዕቃዎቻችሁን የብሱ ላይ አስቀምጡ! በቂ ጀልባዎች አዘጋጅተናል!....... ለመዋኘት አትሞክሩ!" የሜሮዳ ድምፅ ነበር::

ሚራዥ ግን ጀልባ ለመጠበቅ የሚያስችል ትዕግስት አላገኘም፡ እንደጀመረው በዋና ገስግሶ ተሻገረ::

ጌራና ሜሮዳ ተሳምተው ተጠመጠሙበት:: ሌሎችም የማያውቃቸው መነኮሳት ከበቡት::

"የኢትዮጵያ አምላክ ታላቅ ነው!... እንደገና ተመልሳችሁ መጣችሁ!" አሉ አንድ ሽማግሌ መነኩሴ ዕንባ እያነቃቸው:: "ዋሻው ሲፈነዳ የቆሰለውና ከዋሻው ውጭ ገዳሙ ውስጥ እያለን የተረፍነው እንደገና ዋሻውን ስናዘጋጅ ነበር:: ከምድር ውስጡ እሳት ተርፋችሁ የሄዳችሁት አንድ ቀን ተመልሳችሁ እንደምትመጡ ተስፋ ነበረን:: የኢትዮጵያ አምላክ ታላቅ ነው! እንደገና ተመልሳችሁ መጣችሁ:: መጣችሁ!" የሚራዥን ዕርቃን መንኩሴው እጣን በሚሸት መጎናጸፊያቸው ሸፈኑለት:: ዕርቃን መቆሙን ረስቶት ነበር::

"ቁስለኞቹ እንዴት ሆኑ!?" ሚራዥ ቁስለኞቹ ወዳሉበት ገባ፡፡ ዓይኖቹ በዕንባ ጉም ለበሱ፡፡ መናገር አልቻለም፡፡ ሲጻራ ነቅታ ልጇን እያጠባች ነበር፡፡ ብዙው የሰውነትዋ ክፍል ጭንቅላትዋን ጨምሮ በፋሻ በመሸፈኑ ምኗላይ እንደቆሰለች እንኳዋ መለየት አልቻለም፡፡ በዝግታ ከንፈሮቿን ፈለቀቀቻቸው፡፡ ሚራዥ በማያውቀው ስሜት ተወርውሮ አቀፋት፡፡ እንደገና ወደ ኪራኮስ ሮጠ፡፡ ኪራኮስም ከሰመመን ነቅቶ ነበር፡፡

"የሚያምር ልጅ ተወልዷል፡፡... ሚራዥ... ደስ ይላል፡፡ የኔ አባት የሠራውን አፍርሷል፡፡ ሆኖም፣ ሳይፀፀት አልቀረም፣ ማስታወሻውን ያስቀመጠውም ለዛ ሳይሆን አይቀርም፡፡ አባቴ ያፈራረሰውን ስጠግን እኖራለሁ... የሁላችንም እጣ ፈንታ እንዲሁ ሆኗል፡፡"

"አይዞን ኪራኮስ!... አትዘን!... ያለ ውጣ ውረድ የሚመጣ ድል የለም፡፡ አባቶቻችን ክፉም በጎም መሥራታቸው እሙን ነው፡፡ ክፉውን እየጣልን በጎውን እያነሳን እንጓዛለን፡፡ የጥንቱን በመመርመር አሁን ካለው ነባራዊ የዓለም ሂደት ጋር በማዋሀድ ትውልዱን ሥር በሰደደና ጥበብ በተሞላበት ብልሀት በማነፅ ከግልቡ ወደ እውናዊዉ ሥልጣኔ እንመራዋለን፡፡ ትውልድን መገንባት ረጅም ዘመን የሚወስድ ራሱን የቻለ ሂደት ነው፡፡ ይህ መንግሥት በሳምንት የሚላጥ አስፋልት በማንጠፍ፣ በነጋታው የሚፈነቀል ኮብል ስቶን በየስርቻው በመወተፍ፣ ወዲያው የሚናድ ብሎኬት በመደርደር አገር የገነባ ያስመስላል፡፡ አገር የሚገነባው የትውልድ አዕምሮ በእውነተኛ ሀገራዊ ፍቅር ሲታነጽ ነው፡፡ ያለ ሀገር ፍቅር የተሠራውንማ በነጋታው ሲፈርስ አየነው! የኛ ህልም የሀገር ፍቅርን እንደገና እንዲነሳሳ መቆስቆስ ነው፡፡ ህልማችን... ኢትዮጵያ፣... በአፍሪካ ደረጃ እንኳ፣ የደቡብ አፍሪካን ሀብት፣ የናይጀሪያን ተሰሚነት፣ የግብጽን ያህል የፖለቲካ ጫና አሳዳሪነት፣ የእንግሊዝን ያህል የህዝብ አንድነት፣ የአሜሪካን ያህል ተደማጭነት፣ የእስራኤልን ያህል የደህንነትና ወታደራዊ ብቃት እንዲኖራት ማድረግ ነው፡፡ ቀስ በቀስ የሀገራችን የደህንነትና ወታደራዊ ኃይል ከህዝቡ ጋር እንዲቆም ማድረግ ነው፡፡ ሁሉም ነገር የሚጀምረው ራስን ከማወቅ ነው፡፡ ለዚህም ሲባል የማንፈነቅለው ድንጋይ አይኖርም፡፡ አባቶቻችን በ'ኛ የሚያሳኩት ህልም አላቸው፡፡ ህልሞቻችንን ለማስረፅ ጥረታችንን እንቀጥላለን፡፡ እስካሁንም ቢሆን ተፅዕኖ

አልፈጠርንም አይባልም፡፡ የባቡር ዝርጋታው፣ ከፖለቲካ ፍጆታ አልፈው ያደረጉት ነገር የለም እንጂ እኛ መሪዎቻችን ሀገሪቷን በባቡር ከጫፍ ጫፍ ማገናኘት ስንል ያቀድነው ነው፡፡ ሌላም! ሌላም! … ግልቡን ስልጣኔ እንገልበዋለን! ዣንቶዣራ!" ሚራዥ የኪራኮስን እጅ በኃይል ጨበጠው፡፡

"ዣንቶዣራ!" ኪራኮስ አንዳች የተስፋ መንፈስ ወረረው፡፡ "ገና! ገና!...ብዙ የምንመረምረው አለ፡፡ ይሄ ላንተ ነው፡፡" ኪራኮስ ለሚራዥ አንድ የብራና ጥቅል ሰጠው፡፡ ተቀብሎ ተረተረው፡፡ ከዚህ ቀደም አይቷቸው በማያውቅ አያሌ ቃላት የተሞላ ጥቅል፡፡ በየመሀላቸው "ቶ" ፊደል ያለባቸው በአምስት አምስት ፊደላት የተዋቡ ቃላት፡፡ "አባቴ ቀብሯቸው ያገኘኋቸው ቃላት ናቸው፤ እንመረምራቸዋለን፡፡ ውስብስብ የሆነች አስገራሚ ሀገር…" ኪራኮስ ፈገግ አለ፡፡ ሚራዥም ፈገግ አለ፡፡ ሁለቱም ቀና ሲሉ አያሌ ህዝብ ከቧቸው ነበር፡፡

ሚራዥ በማያውቀው የደስታ ስሜት ጮኸ፡፡ እሱን ተከትሎም ዋሻው በጩኸት ተናጋ…

"ህጻናት ከሚደርሱበት ቦታ ይቀመጥ!"

አስተያየተዎን ከዚህ በሚከተለው አድራሻ ቢልኩ ይደርስለወታል፡፡

ይስማዕከ ወርቁ
ፖ.ሣ.ቁ 17486
አዲስ አበባ
ኢትዮጵያ
E-mail:-ramatohara@gmail.com